


# በአዲስ አበባ ከተማ ግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን

# ADDIS ABABA CITY CONSTRUCTION PERMIT AND CONTROL AUTHORITY

## የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥ እና ክትትል ማስፈፀሚያ መመሪያ እና ስታንዳርድ ቁጥር 01/2015




ጥቅምት 01/2015
አዲስ አበባ

አዲስ አበባ ከተማ የኢ.ፌ.ዴ.ሪ መንግስት ርዕሰ ከተማ፣ የአፍሪካ መዲና እና የተለያዩ ዓለም አቀፍ፣ የመንግስትና የግል ተቋማት መቀመጫ እንደ መሆኗ ከተማዋ ፈጣን የማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ እድገት ላይ ትገኛለች። ይህን ተከትሎ በመጠን፣ በዓይነትና በቴክኖሎጂ አጠቃቀም እያደገና ተለዋዋጭ ሆኖ የመጣውን የውጭ ማስታወቂያ/Out-door Advertising/ አገልግሎት አሰጣጥ ቀልጣፋና ውጤታማ በማድረግ በሕግና ሥርዓት መምራት በማስፈለጉ፣

በውጭ ማስታወቂያ ዘርፍ ጤናማ ውድድር እንዲኖር በማድረግ ከዘርፉ የሚገውኘን ከፍተኛ ኢኮኖሚያዊ ፋይዳ/ገቢ የሚያስገኝና ለዜጎች የስራ ዕድል የሚፈጥር በመሆኑ ለዘርፉ ምቹ ሁኔታን መፍጠር በማስፈለጉ፣

የውጭ ማስታወቂያ በሥርዓት ካልተመራ የሕብረተሰቡን መብትና ጥቅም እንዲሁም የአገራችንና ከተማችንን ገጽታ ሊጎዳ ስለሚችል የአካባቢ ጥበቃን፣ የትራፊክ እንቅስቃሴን፣ የከተማችንን ውበትና ገጽታ ለመጠበቅ የጥራት ስታንዳርድ ማውጣት አስፍላጊ በመሆኑ፣ እንዲሁም የማስታወቂያ ወኪሎች፣ አሰራጮችና አስነጋሪዎችን መብት እና ግዴታን በግልጽ መወሰን በማስፈለጉ፣

የግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለሰልጣን በኢትዮጵያ ስለማስታወቂያ የወጣ አዋጅ ቁጥር 759/2004 አንቀጽ 36(3) ለአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር በተሰጠ ሥልጣንና ተግባር እንዲሁም የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር አስፈጻሚ አካላት ማቋቋሚያ አዋጅ ቁጥር 74/2014 እና በውጭ ማስታወቂያ ደንብ ቁጥር 131/2014 በተደነገገው መሰረት ለባለስልጣኑ በተሰጠው ሥልጣንና ተግባር መሰረት ይህን መመሪያ እና ስታንዳርድ አውጥቷል።

## ክፍል አንድ

### ጠቅላላ

#### 1.2 አጭር ርዕስ

ይህ መመሪያ "የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥና ክትትል ማስፈፀሚያ መመሪያ እና ስታንዳርድ ቁጥር 01/2015" ተብሎ ሊጠቀስ ይችላል።

#### 1.3 ትርጓሜ

የቃሉ አገባብ ሌላ ትርጉም የሚያሰጠው ካልሆነ በስተቀር በዚህ መመሪያ ውስጥ፥

1. "**ሚኒስቴር**"፥ ማለት የኢፌዲሪ የኮንስትራክሽን ሚኒስቴር ነዉ።
2. "**ከተማ**"፥ ማለት የአዲስ አበባ ከተማ ነዉ።
3. "**አስተዳደር**"፥ ማለት የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ነዉ።
4. "**ባለስልጣን**"፥ ማለት የግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን ነው።
5. "**ጽ/ቤት**"፥ ማለት በክ/ከተማና የወረዳ ግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ጽ/ቤት ነው።
6. **"የደንብ ማስከበር አገልግሎት"**፥ ማለት በአዲስ አበባ ከተማ ደንብ ማስከበር አገልግሎትና በክፍለ ከተማ እና ወረዳ የሚገኘው ደንብ ማስከበር ጽ/ቤት ነው።
7. **"ማስታወቂያ"** ማለት የምርት ወይም የአገልግሎት ሽያጭ እንዲስፋፋ ወይም ስም፣ አርማ፣ የንግድ ምልክት ወይም ዓላማ እንዲተዋወቅ በውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ መንገድ አማካኝነት የሚሰራጭ የንግድ ማስታወቂያ ሲሆን የሕዝብ አገልግሎት ማስታወቂያንና የግል ማስታወቂያን ይጨምራል።
8. **"የማስታወቂያ ስራ"** ማለት ማስታወቂያ ማዘጋጀትን፣ ማሠራጨትን እና ከማስታወቂያ ጋር ተያያዥነት ያለውን ሌላ ሥራ የሚያካትትሥራ ነው።
9. **"የውጭ ማስታወቂያ/ማስተዋወቅ ሥራ"**፥ ማለት አንድ ሰው አርማውን፣ ምልክቱን፣ ምርቱን፣ አገልግሎቱን፣ ስሙን፣ አድራሻውን፣ ወይም አላማውን እንዲሁም ክስተትን የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ ዘዴዎችን በመጠቀም ማስታወቂያውን በከፊል ወይም በሙሉ በመግለጽ ለህዝብ የሚነገር ወይም ለእይታ ግልጽ በሆነ ቦታ የሚካሄድ የማስታወቅ ስራ ነው።
10. **"የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ ዘዴ/መንገድ"**፥ ማለት

    ሀ) በቢል ቦርድ፣ በማስታወቂያ ሰሌዳ፣ በኤሌክትሮኒክ ስክሪን ወይም በተንቀሳቃሽ ምስል የሚሰራጭ፣

ለ) በሕንጻ፣ በግድግዳ፣ በጣራ ወይም በማናቸውም ስትራክቸር ወይም በትራንስፖርት ተሽከርካሪ፣ በተንሳፋፊ ፊኛ ወይም መሰል ነገር ላይ የሚሳል፣ የሚፃፍ፣ የሚለጠፍ ወይም የሚተከል፣

ሐ) በተንጠልጣይ ነገር፣ በባነር፣በፖስተር፣ በስቲከር፣ በተባዛ በራሪ ወረቀት፣ በብሮሽር፣ ሊፍሌት፣ ፍላየር የሚሰራጭ፣

መ) በድምጽ ካሴት፣ በድምፅ ማጉያ መሳሪያ የሚሰራጭ፣ ወይም

ሠ) በሌላ መሰል ማሰራጫ መንገድ አማካኝነት የሚሰራጭ ማስታወቂያ ሲሆን የመንገድ አቅጣጫ ጠቋሚ፣ የትራፊክና የአውቶቢስ ፌርማታ ምልክትን፣ የመንገድ ስምን ወይም ቁጥርንና መሰል የሕዝብ አገልግሎት መረጃ ሰጪ ምልክቶችን አይጨምርም።

11. **"የማስታወቂያ ወኪል"፥** ማለት አግባብ ባለው የሀገሪቱ ህግ መሠረት ፈቃድ አውጥቶ በማስታወቂያ ስራ ላይ የተሰማራ ሰው ነው።
12. **"የውጭ ማስታወቂያ አሰራጭ"፥** ማለት እንደ አንድ የንግድ ዘርፍ የንግድ ሥራ ፈቃድ በማውጣት የማስታወቂያ ዘዴዎችን በመጠቀም እንዲሁም የትራንስፖርት ተሽከርካሪ፣ የህንጻ አካልን የማስታወቂያ ሰሌዳ ፍሬምን፣ የማስታወቂያ መለጠፊያ ሳጥንን ወይም ቢልቦርድ ተክሎ በማስለጠፍ ወይም ማናቸውንም መሰል አገልግሎትን ለውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫነት እንዲውል በማድረግ የውጭ ማስታወቂያ የማሰራጨት አገልግሎት የሚሰጥ ሰው ወይም ድርጅት ነው።
13. **"የማስታወቂያ አስነጋሪ"፥** ማለት ምርቱ፣ አገልግሎቱ፣ ስሙ፣ አርማው፣ የንግድ ምልክቱ ወይም አላማው የሚተዋወቅለት ሰው ወይም ድርጅት ማለት ነው።
14. **"ፈቃድ ሰጪ አካል"፥** ማለት የግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን እና በሥሩ ያሉ የክ/ከተማና የወረዳ ጽ/ቤቶችን ነው።
15. **"መሪ ፕላን"፥** ማለት የአዲስ አበባ ከተማ መዋቅራዊ ፕላን ወይም የአካባቢ እድገት /LDP/ ፕላን ነው።
16. **"የህዝብ አገልግሎት"፥** ማለት መንግስታዊ ተቋማት በሕግ የተሰጣቸውን ኃላፊነት ለመወጣት የሚፈለግባቸውን የስብሰባ ጥሪ፣ ቅስቀሳ የመሳሰሉትን ማድረግን ያጠቃልላል።
17. **"ዋና መንገድ"፥** ማለት በከተማው መሪ ፕላን ላይ ዋና መንገድ (PAS) ተብሎ የተጠቀሰ መንገድ ነው።
18. **"ዋና ዋና መንገድ"፥** ማለት በከተማው መሪ ፕላን ላይ ዋና መንገድ (PAS) ወይም ዋና መጋቢ መንገድ (SAS) ወይም ቀለበት መንገድ (RR) ተብሎ የተጠቀሰ መንገድ ነው።
19. **"የውጭ ማስታወቂያ ሠሌዳ"፥** ማለት በኤሌክትሪክ ወይም በብርሃን የሚሠራ ማስታወቂያ የሚለጠፍበት ሰሌዳ ወይም የማስታወቂያ ሥራ የሚካሄድበት ወይም የሚታይበት በተለጣፊ ጽሑፍ፣ በተንቀሳቃሽ ምስል፣ በስእል ወይም በሌላ ዘዴ የማስታወቂያ ሥራ የሚሠራበት ሠሌዳ ነው።
20. **"አደባባይ"፥** ማለት በመንገድ መሃል በትራፊክ መሸጋገሪያና ማዟዟሪያ የሚያገለግል ሆኖ ለተለያዩ ሀውልቶች፣ ቅርጻ-ቅርፆች፣ የውኃ ፋውንቴን ግንባታዎችና ለእጽዋት መትከያ የተተወ አረንጓዴ ቦታ ነው።
21. **"አደባባይ ዙሪያ"** ማለት በአደባባይ ዙሪያ በሚገኝ የእግረኛ መንገድ በውጭ በኩል ያለ ለውጭ ማስታወቂያ መትከያ የሚያገለግል ቦታ ነው።
22. **"የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጨት"፥** ማለት የውጭ ማስታወቂያ መንገዶችን በመጠቀም ማስታወቂያ መትከል፣ መለጠፍ፣ መሳል፣ መፃፍ፣ ማስቀመጥ ወይም በማናቸውም መንገድ ማሰራጨትንና በድምፅ ማስተዋወቅን ይጨምራል።
23. **"ከህዝብ መልካም ፀባይ ጋር የሚቃረን መልዕክት"** ማለት ፈቃድ ከተሰጠበት ዉጭ ሆኖ ህዝብን ለአመጽ የሚያነሳሳ፣ ከህብረተሰቡ መልካም ጸባይ እና እሴቶች ጋር የማይጣጣም መልእክት ነው።

24. **“ስፖንሰር”**፥ ማለት ማንኛውም ማስታወቂያ ማሰራጫ መንገድን በመጠቀም ማስታወቂያ እንዲተላለፍ ገንዘብ በቀጥታ ወይም በተዘዋዋሪ የተከፈለበት ወይም የክፍያ ቃል የገባ ሰው ወይም ተቋም ማለት ነው።

25. **“የሕዝብ አገልግሎት ማስታወቂያ”**፥ ማለት ለሕዝብ ጥቅም ሲባል በውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ መንገድ አማካኝነት የሚሠራጭ መልዕክት ነው።

26. **“የግል ማስታወቂያ”**፥ ማለት በውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ መንገድ አማካኝነት የሚሰራጭ የአፋልጉኝ እና ሌላ መሰል ማስታወቂያን ያካትታል።

27. **“አዋጅ”**፥ ማለት የማስታወቂያ አዋጅ ቁጥር 759/2004 ማለት ነው።

28. **“ደንብ”**፥ ማለት የማስታወቂያ ደንብ ቁጥር 131/2014 ማለት ነው።

29. **“ደንብ”**፥ ማለት የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር የአገልግሎት ክፍያ ለመወሰን የወጣ ደንብ ቁጥር 117/2013 ነው።

30. **“ባለቤት”**፥ ማለት የማስታወቂያ ስራ ድርጅት ባለቤት ወይም ህጋዊ ወኪል ነው።

31. **“ሰው”**፥ ማለት የተፈጥሮ ሰው ወይም በሕግ የሰውነት መብት/ዕውቅና የተሰጠው አካል ነው።

32. ማንኛውም በወንድ ፆታ የተገለጸው የሴትንም ይጨምራል።

### 1.4 የተፈጻሚነት ወሰን

ይህ መመሪያ እና ስታንዳርድ በአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ክልል ውስጥ በውጭ ማስታወቂያ ተግባር በሚመለከት በማናቸውም ሥራዎች ላይ ተፈጻሚ ይሆናል።

## ክፍል ሁለት

## /ስለ ውጭ ማስታወቂያ መመሪያ/

## የውጭ ማስታወቂያ ሥራ መብት፣ ፈቃድ፣ ደረጃ እና ስርጭት

### 1.1 በውጭ ማስታወቂያ ሥራ የመሰማራት መብት

2.1.1 ማንኛውም ዜግነቱ ኢትዮጵያዊ የሆነ ግለሰብ ወይም በኢትዮጵያ ሕግ መሠረት የተቋቋመና በካፒታሉ ውስጥ የውጭ አገር ዜጋ ድርሻ የሌለበት የንግድ ድርጅት በውጭ ማስታወቂያ ሥራ የመሰማራት መብት ይኖረዋል፣

2.1.2 በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 2.1.1 የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ በትውልድ ኢትዮጵያዊ የሆነ የውጭ አገር ዜጋ በውጭ ማስታወቂያ ሥራ ላይ የመሰማራት መብት ይኖረዋል።

### 1.2 የውጭ ማስታወቂያ ሥራ ፈቃድ

ማንኛውም በውጭ ማስታወቂያ ዘርፍ መሰማራት የሚፈልግ ሰው፥

1. የውጭ ማስታወቂያ አገልግሎት የንግድ ስራ ፍቃድ ማውጣት አለበት፣
2. ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ ወኪል በዚህ መመሪያ አንቀጽ 2.1 የተደነገገውን አሟልቶ በውጭ ማስታወቂያ ስራ ለመስራት የውጭ ማስታወቂያ አገልግሎት የንግድ ሥራ ፈቃድ ማውጣት አለበት፣
3. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ (1) እና (2) የተደነገገው ቢኖርም የማስታወቂያ አስነጋሪው የራሱን ድርጅት ወይም ምርት ወይም አገልግሎት ለማስተዋወቅ የማስታወቂያ ንግድ ሥራ ፈቃድ፣ የሙያ ብቃት ማረጋገጫ ሰርተፍኬት ማውጣት ሳያስፈልገው ከሚመለከተው አካል የውጭ ማስታወቂያ ይዘቱን በማረጋገጥ እና ከባለስልጣኑ የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ በማውጣት ማስተዋወቅ ወይም ማሰራጨት ይችላል፣ ሆኖም የውጭ ማስታወቂያ አስነጋሪው ይህን ስራ መስራት የሚችለው፥

    ሀ. በራሱ የመሬት ይዞታ ውስጥ ሲሆን፣

    ለ. በራሱ የንግድ መኪኖች ላይ ሲሆን፣

    ሐ. ለንግድ ስራ ከሌላ አካል በተከራየው የንግድ ቦታ ወይም የንግድ ቤት ላይ፣

መ. ሌሎች ለንግድ ስራ በተከራዩት ቦታ ወይም ቤት ላይ የራሱን ምርት/ አገልግሎት ለማስተዋወቅ የተስማሙበት ውል ሲኖር፣

4. ማንኛውም በውጭ አገር ተዘጋጅቶ ወደ ኢትዮጵያ የሚገባ ማስታወቂያ እንዲሰራጭ ሊደረግ የሚችለው በማስታወቂያ ወኪል አማካኝነት ብቻ ነው።

### 1.4 ስለውጭ ማስታወቂያ የጥራት ደረጃ

ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ ከመሰራጨቱ በፊት በመመሪያውና በስታንዳርዱ የተቀመጡትን መስፈርቶች የሚያሟላ መሆን አለበት።

### 1.5 ስለውጭ ማስታወቂያ ሥርጭት

በማንኛውም ሁኔታ የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጨት የሚቻለው በባለስልጣኑ እና በስሩ ባሉ በክ/ከተማ እና በወረዳ ፅ/ቤቶች ፈቃድ ብቻ ነው።

## ክፍል ሶስት

## የውጭ ማስታወቂያ ስርጭትን ስለማቋረጥ

1. ማንኛውም ማስታወቂያ ከተፈቀደለት ይዘት ውጪ ሲሆን፣ ለህግ ወይም ለህዝብ ሞራል ተቃራኒ የሆነ መልእክት እንደሚያስተላልፍ በሚመለከተው አካል ከተረጋገጠ፣ በቅድሚያ የማስታወቂያው ባለቤት እስከ አንድ ቀን ወይም በ24 ሰዓት የጊዜ ገደብ ውስጥ እንዲያነሳ የማስጠንቀቂያ ጽሁፍ እንዲደርሰዉ በማድረግ የማስታወቂያ ሥራው ይቋረጣል፣

2. በደረሰው ማስጠንቀቂያ መሰረት ለማንሳት ፈቃደኛ ካልሆነ ባለስልጣኑ በራሱ ወጪ አንስቶ ንብረቱን በመውረስ ለማንሳት ያወጣውን ወጪ ከባለቤቱ በህግ ይጠይቃል ከዚህ በተጨማሪም በከተማው ክልል በማንኛውም ቦታ ምርቱንም ሆነ አገልግሎቱን የማስተዋወቅ ስራ ለመስራት ጥያቄ ቢያቀርብ ለአንድ ዓመት እንዳይሳተፍ ይደረጋል፣

3. በማንኛውም ወቅት ሰሌዳው የተተከለበት ቦታ ለሌላ አገልግሎት ሲፈለግ ከፈቃድ ሰጪው በሚሰጠው የጊዜ ገደብ መሰረት የማስታወቂያ ሰሌዳው ባለቤት እንዲያነሳ በማድረግ ማስታወቂያዉ ይቋረጣል፣

4. ቦታዉ ለልማት ወይም ለማናቸውም የሕዝብ አገልግሎት ወይም ለሌላ አገልግሎት ተፈልጎ ሰሌዳዉ ሲነሳ የኪራይ ወይም የአገልግሎት ዘመኑ ያልተጠናቀቀ ከሆነ ለባለፈቃዱ የቀሪ ወራት ሂሳብ ተሰልቶ ይመለስለታል ወይም ምትክ ቦታ ይሰጠዋል፣ ሆኖም የኪራይ ዘመኑ የተጠናቀቀ ከሆነና በቀጣይ ማስተዋወቅ ከፈለገ ጥያቄው በአዲስ መልክ ይስተናገዳል፣

5. ማንኛውም ሰው የተፈቀደለትን ማስታወቂያ ሥራ ለማቋረጥ ሲወስን ለፈቃድ ሰጪው በአስር ቀናት ውስጥ በጽሁፍ በማሳወቅ ማስታወቂያዉ እንዲቋረጥ ማድረግ ይኖርበታል፣ ለቀሪው የውል ጊዜ የተከፈለው ክፍያ ሳይመለስ ማስታወቂያዉ ይቋረጣል፣

6. ይህ መመሪያ ከመውጣቱ በፊት በባለስልጣኑ ፈቃድ ተሰጥቷቸው ከዚህ መመሪያ ወይም ከስታንዳርድ ውጭ የተሰሩ ማስታወቂዎች በአምስት ቀናት ቅድሚያ ማስጠንቀቂያ እንዲነሱ ያደርጋል፣ በተሰጣቸው የጊዜ ገደብ ካላነሱ በራሱ ወጪ አንስቶ ንብረቱን በመውረስ ለማፍረስ ያወጣውን ወጪ በህግ ይጠይቃል።

7. በአንቀጽ3.4 የተደነገገው ቢኖርም ምትክ ቦታ የሚሰጠው ቀሪው የሊዝ ዘመን ከአንድ አመት በላይ ከሆነ ነው፤ ከአንድ አመትና ከአንድ አመት በታች የቀረው ከሆነ ለማስታወቂያው የከፈለው የአገልግሎት ክፍያ ይመለስለታል፤ ወለድ አይታሰብበትም

8. ማስታወቂያው እስከ ተነሳበት ጊዜ ድረስ የሚፈለግበትን የአገልግሎት ክፍያ ይኸው የጊዜ ገደብ ከማብቃቱ በፊት በሙሉ መክፈሉን የሚያረጋግጥ ሰነድ ለፈቃድ ሰጪው አካል በማቅረብ ምዝገባውን አሰርዞ ማስረጃ መውሰድ አለበት፤ ፈቃድ ሰጪው አካልም ሁኔታውን አጣርቶ በቀረበለት ጥያቄ መነሻ በአስር ቀናት ውስጥ ለአመልካቹ ማስረጃ መስጠት አለበት

## ለሕዝብ ጥቅም ቅድሚያ ስለመስጠት

1. ለግንባታ፣ ለልማት ወይም ለማናቸውም የሕዝብ አገልግሎት የሚጠቅም ሆኖ ሲገኝ ፈቃድ በማግኘት የተተከለ ወይም የተለጠፈ የውጭ ማስታወቂያን ለማስታወቂያ አስነጋሪው በማሳወቅና ተለዋጭ ቦታ ወይም የቀሪ ወራት ሂሳብ ተሰልቶ እንዲሰጠው በማድረግ በሚሰጠው የጊዜ ገደብ መሰረት የማስታወቂያው ባለቤት ማስታወቂያውን እንዲያነሳ በማድረግ ማስታወቂያው ስርጭት ይቋረጣል፣ በዚህ ሁኔታ ለተነሳ ማስታወቂያ ካሳ አይከፈልም፣
2. ከንግድ እና ከሕዝብ አገልግሎት ማስታወቂያ ስርጭት ጋር በተያያዘ ደንቡን እና መመሪያን በማስፈፀም ሂደት ውስጥ ተነፃፃሪ ፍላጎቶች ሲኖሩ ለሕዝብ አገልግሎት ማስታወቂያ ቅድሚያ መሰጠት ይኖርበታል።

## ለውጭ ማስታወቂያ ቦታ ስለመፍቀድ

ለውጭ ማስታወቂያ የሚሰጡ ቦታወች በሁለት መንገድ ሊፈቀድ ይችላል። መንግስት ይዞታ የሆነ መሬት እና ንብረት ላይ የውጭ ማስታወቂያ ስራ በዋነኛነት የሚሰራበት ሲሆን አገልግሎቱን ለማሳለጥ በሚያመች ሁኔታ ለማከናወን በቀጥታ በምደባ እና በጨረታ የሚፈቀድ ይሆናል።

**1. በጨረታ ለውጭ ማስታወቂያ ስራ የሚሰጡ ቦታወች**

ሀ. ለውጭ ማስታወቂያ መትከያነት በጨረታ የሚሰጡ ቦታዎች በፍትሃዊነትና በግልፀኝነት መስጠት ይኖርባቸዋል፣

ለ. በዋና መንገድ ላይ ለውጭ ማስታወቂያ መትከያ የተዘጋጁ ቦታዎች እና ሌሎች የከተማው አስተዳደሩ ንብረት የሆኑና ለውጭ ማስታወቂያ መትከያ የተዘጋጁ ቦታዎች በጨረታ የሚሰጡ ይሆናል፣

ሐ. ባለስልጣኑ በወረቀት የሚዘጋጅ ማስታወቂያ ሊለጠፍበት የሚችል የጋራ የማስታወቂያ ሰሌዳ እንደ አስፈላጊነቱ በጨረታ ወይም በቀጥታ ያለውድድር ሊሰጥ ይችላል፣

መ. የውል ጊዜው የተጠናቀቀ የውጭ ማስታወቂያ መትከያ ቦታ የሚተላለፈው በድጋሚ ጨረታ በማውጣት ይሆናል፣

ሠ. በዋናነት ጨረታ የሚወጣባቸው ቦታወች፥

1. ዋና መንገዶች ላይ የሚገኙ ክፍት ቦታወች፣
2. በትልልቅ አደባባዮች ዙሪያ፣
3. በከተማ እና በክ/ከተማ ደረጃ በሚገኙ ፓርኮች፣
4. የቀላል ባቡር መስመር ድልድዮች፣
5. በቀላል ባቡር እና በከተማ አውቶቢስ ላይ የሚለጠፍ/የሚሰቀል/የሚተ ማስታወቂያ፣
6. ቁጥራቸው 50 እና ከዚያ በላይ የሆኑ የመንግስት ተሽከርካሪወች በአንድ ጊዜ ለማስታወቂያ ስራ ሲቀርቡ፣

**2. በቀጥታ ለውጭ ማስታወቂያ ስራ በምደባ የሚፈቀዱ ቦታዎች**

ከዋና መንገድ ውጭ በሆኑ መንገዶች ላይ ለሚተከሉ የውጭ ማስታወቂያዎች እንደ አስፈላጊነቱ ያለ ጨረታ በአመልካቹ ጥያቄ መሰረት ፈቃድ ይሰጣል። እንዲሁም በሚከተሉት ቦታወች፣ ቋሚ አካል እና ተሽከርካሪወች ላይ በምደባ ይሰጣል።

ሀ. ለአቅጣጫ ጠቋሚ ምልክቶች በማንኛውም ቦታ እስከ 500 ሜትር ራዲየስ፣

ለ. የቀላል ባቡር መስመር ኮንክሪት ምሰሶወች ላይ፣

ሐ. የእግረኛ እና መኪና መሸጋገሪያ ድልድዮች ላይ፣

መ. ማንኛውም ባለቤትነታቸው የመንግስት የሆኑ ንብረቶች ላይ፣

ሠ. ጨረታ ከሚወጣባበት መሬት ውጭ በአሉት ክፍት ቦታዎች፣

ረ. አዳዲስ ቴክኖሎጂ በመጠቀም ለዘርፉ የላቀ ፋይዳ እንዲኖረው ለሚያደርጉ፣ የተሸለ ካፒታል ለሚያቀርቡ፣ የተሻለ የስራ እድል ለሚፈጥሩ እና በተሻለ የፕሮጀክት ፕሮፖዛል ማሳየት ለሚችሉ አካላት በልዩ ሁኔታ በባለስልጣኑ ማኔጅመንት ሲወሰን፣

ሰ. ለልዩ ልዩ ፕሮግራሞች/ሁነቶች ለአጭር ጊዜ ለሚፈቀድ የውጭ ማስታወቂያ፣

## ክፍል አራት

## የውጭ ማስታወቂያ ይዘት፣ ቋንቋ እና ፊደል አጠቃቀም

### 1.6 የውጭ ማስታወቂያ ይዘትና አቀራረብ

1. **ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ ይዘት፥**

   ሀ. ማናቸውንም ሕግ ወይም መልካም ሥነ-ምግባርን የማይፃረር አሳሳች ወይም ተገቢ ካልሆነ አገላለጽ ነጻ የሆነ፣

   ለ. የኅብረተሰቡን ማኀበራዊና ባህላዊ እሴትን የሚያከብርና ሕጋዊ ጥቅም የማይጎዳ፣

   ሐ. የሚተዋወቀው ምርት/አገልግሎት እውነተኛ ባህሪ/ጥቅም፣ ጥራትና መሰል መረጃዎችን የሚገልጽ መሆን አለበት፣

   መ. የሌሎችን ሰዎች ምርት ወይም አገለግሎት የማያንቋሽሽ፣

   ሠ. የአገርን ክብርና ጥቅም የሚጠብቅ፣

   ረ. የሙያ ሥነ ምግባርን የሚያከብር ይዘትና አቀራረብ ያለው መሆን አለበት፣

   ሸ. ለየት ያለ ባህሪ ያላቸው ምርቶች ወይም አገልግሎቶች ህብረተሰቡን የማይጎዳ መሆኑን ከሚመለከተው የመንግስት አካል ማረጋገጫ መቅረብ አለበት፣

2. **የሚከተሉት የውጭ ማስታወቂያዎች ሕግን ወይም መልካም ሥነ-ምግባርን የሚጻረር ይዘት ወይም አቀራረብ እንዳላቸው ሆነው ይቆጠራሉ፥**

   ሀ) ቋንቋን፣ ፆታን፣ ብሔር ብሔረሰብን፣ ሙያን፣ ሐይማኖትን፣ እምነትን፣ ፖለቲካዊ ወይም ማህበራዊ አቋምን አስመልክቶ የሰው ልጅን ስብዕና፣ ነጻነት ወይም እኩልነት የሚጻረር ምስልን የያዘ፣

   ለ) የግለሰብን፣ የብሔር ብሔረሰብን ወይም የህዝብን መልካም ሥነ ምግባር ወይም ሰብአዊ ክብርን እንዲሁም የድርጅትን መልካም ስምና ዝና የሚያጐድፍ፣

   ሐ) ብሔራዊ ወይም የክልል ሰንደቅ ዓላማን፣ አርማን፣ ብሔራዊ መዝሙርን ወይም ገንዘብን የሚያንቋሽሽ ወይም የሚያዋርድ፣

   መ) የአካል ጉዳተኛን፣ የኤች አይ ቪ/ኤድስ ቫይረስ በደሙ ውስጥ ያለበትን ወይም በሌላ ህመም የተያዘ ሰውን ክብርና ሥነ ልቦና የሚነካ፣

   ሠ) በኅብረተሰቡ መካከል አመጽ፣ የሀይል ተግባር፣ ሽብር፣ ግጭት ወይም የፍርሃት ስሜት እንዲፈጠር የሚያነሳሳ፣

   ረ) የኅብረተሰቡን አካላዊና አእምሮአዊ ጤንነት ወይም ደህንነት ለጉዳት የሚያጋልጥ ድርጊት እንዲፈፀም የሚያነሳሳ፣

   ሰ) አግባብነት ያለው የመንግሥት አካል የሚወሰነውን የድምጽ መጠን በመተላለፍ በማናቸውም ዓይነት የድምጽ ማጉያ አማካይነት አካባቢን በከፍተኛ ድምጽ በመበከል የሚነገር፣

   ሸ) ለመልካም ፀባይ ተቃራኒ የሆነ የጽሁፍ መልዕክት፣ ምስል፣ ሥዕላዊ መግለጫ ወይም መሰል አቀራረብን የያዘ፣

   ቀ) የግለሰብን ስም፣ ምስል ወይም ፎቶግራፍ ግለሰቡ ሳይፈቅድ የሚጠቀም ወይም በህግ ጥበቃ የሚደረግለትን የኪነ-ጥበብ ወይም የፈጠራ ሥራ የሚመለከተው ሰው ሳይፈቅድ የሚጠቀም፣

   በ) ለትራፊክ ደህንነት ወይም ለአካባቢ ጥበቃ ተጻራሪ የሆነ፣

   ተ) የመከላከያ ሠራዊት/የፖሊስ የደንብ ልብስን ወይም ምልክትን በመጠቀም የሚቀርብ የንግድ ማስታወቂያ፣

ቸ) በሌላ ህግ የተከለከለ ይዘት ወይም አቀራረብ የያዘ ወይም ማንኛውም ህግ እንዲጣስ የሚያነሳሳ የውጭ ማስታወቂያ፣

**3. የሚከተሉት ይዘት ያላቻው ማስታወቂያዎች በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ በውጭ ማስታወቂያ ማሰራጨት የተከለከለ ነው፥**

ሀ) አግባብ ባለው የመንግሥት አካል በአደንዛዥ ዕጽነት የተመደበን ማናቸውንም ዕፅ የሚመለከት፣

ለ) ያለሐኪም ትዕዛዝ የማይሰጥ ወይም በጥቅም ላይ የማይውል መድሀኒትን ወይም የህክምና መገልገያን ተጠቃሚው በቀጥታ እንዲጠቀም የሚገፋፋ፣

ሐ) ናርኮቲክ መድሐኒትን ወይም ሳይኮቴራፒክ ንጥረ ነገርን የሚመለከት፣

መ) የጦር መሳሪያ ማስታወቂያ፣

ሠ) የቁማር ማስታወቂያ፣

ረ) የህገ ወጥ ምርት ወይም አገልግሎት ማስታወቂያ፣

ሰ) የአራጣ አበዳሪ ማስታወቂያ፣

ሸ) የጥንቆላ ማስታወቂያ፣

ቀ) የሲጋራ ወይም የሌሎች የትምባሆ ውጤቶች ማስታወቂያ፣

በ) የፖለቲካ ፓርቲ ሆኖ ከተመዘገበ አካል ውጭ የሚደረግ የፖለቲካ ግብ ያለው ማስታወቂያ፣

ተ) የጫት፣ የሺሻ ማስታወቂያ፣

ቸ) የአልኮል ማስታወቂያ፣

ኀ) ሌሎች በህግ የተከለከሉ ማስታወቂያዎች።

4. **በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 8(3)(በ)** የተደነገገው አግባብ ባለው ህግ መሠረት ተመዝግቦ የሚንቀሳቀስ የፖለቲካ ድርጅት ወይም የምርጫ ዕጩ ተወዳዳሪ በምርጫ ወቅት የሚያሰራጨውን የምርጫ ውድድር ማስታወቂያ እንዲሁም የፖለቲካ ድርጅት የሚያሠራጨውን የአድራሻ ለውጥ፣ የሰብሰባ ጥሪ እና መሰል ማስታወቂያን የሚከለክል አይሆንም።

**5. የሰነዶች አቀራረብ**

ማንኛውም የውጭ የማስታወቂያ ሠሌዳ ወይም ቢል ቦርድ ወይም በኤሌክተሮኒክስ ስክሪን በተንቀሳቃሽ ምስል ለሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ ጠያቂ ለጥያቄ ሲቀርብ የሚከተሉትን ሁኔታዎች በዋናነት ማሟላት አለበት

ሀ. የማስታወቂያ ሠሌዳ ግንባታ ፈቃድ ለማግኘት የተሟላ የዲዛይን ንድፍ፣

ለ. የማስታወቂያ ሠሌዳ ፈቃድ ጥያቄ ሲቀርብ ከማመልከቻው በተጨማሪ በኤሌክትሪክ የሚጠቀም ከሆነ የኤሌክትሪክ ምንጩንና መጠኑን በመጥቀስ መቅረብ ይኖርበታል፣

ሐ. የሚተዋወቀው የውጭ ማስታወቂያ የጽሁፍ፣ የምስል ወይም የቅርጽ ንድፍ፣

መ. ስለሚተዋወቀው ምርት ወይም አገልግሎት ወይም የድርጅት መልክት ሙሉ ይዘትየሚገልጽ  ማመልከቻ፣

ሠ.  የታደሰ የንግድ ፈቃድ፣ የብቃት ማረጋገጫ ሰርቲፊኬት፣ መንግሥታዊ ያልሆኑ ድርድቶች የተመዘገቡበትን የምዝገባ ወረቀት እና የታደሰ የስራ ፈቃድ ማቅረብ አለባቸው፣ ማስታወቂያውን ለማሰራጨት የተለየ ማረጋገጫ ፈቃድ የሚያስፈልገው ከሆነ ከሚመለከተለው አካል ማረጋገጫ ደብዳቤ ማቅረብ ይኖርበታል።

**1.7 የውጭ ማስታወቂያ ቋንቋ እና ፊደል አጠቃቀም**

በማናቸውም መንገድ የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ፥

1. በአገር ውስጥ ቋንቋ ወይም ፊደል የተጻፈ መሆን ይኖርበታል፣

2. በውጭ ቋንቋ ወይም ፊደል ጭምር የተጻፈ ከሆነ የአገር ውስጥ ቋንቋው ወይም ፊደሉ ከውጭው ቋንቋ ወይም ፊደል አስቀድሞ ወይም ከላይ ሆኖ የተጻፈ መሆን አለበት፣

3. በውጭ ቋንቋ ተተርጉሞ የቀረበ የውጭ ማስታወቂያ አቻ ትርጉም ከሕጋዊ ተርጓሚ ተቋም መቅረብ አለበት፣

4. ከውጭ ቋንቋ የተወሰደው ቃል ማስታወቂያው በተሰራጨበት የአገሪቱ ቋንቋ ፍቺ ከሌለው በቀር የሀገር ውስጥ ቋንቋ ከውጭ አገር ቋንቋ ጋር በማቀላቀል በውጭ ማስታወቂያ ማሰራጨት የተከለከለ ነው። ሆኖም ይህ ድንጋጌ የንግድ ስምና ምልክትን በውጭ ቋንቋ ከመጠቀም የሚያግድ አይደለም፣

5. በዚህ አንቀፅ ከንዑስ አንቀፅ 1-4 የተመለከተው ድንጋጌ፥

   ሀ) በተባዙ የበራሪ ወረቀት ማስታወቂያዎች ወይም በብሮሸር፣ በሊፍሌት፣ በፍላየር ወይም በወረቀት ላይ በሚሰራጭ ማስታወቂያ፣

   ለ) በምርት ማሸጊያ ወይም መያዣ ላይ በሚሰራጭ ማስታወቂያ፣

   ሐ) በዲፕሎማቲክ እና መሰል አለም አቀፍ ተቋማት በሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ ላይ ተፈፃሚ አይሆንም።

## ክፍል አምስት

## የውጭ ማስታወቂያ የጥራት ደረጃና ብቃት፣ ስርጭት እና የአገልግሎት ክፍያ

### 1.8 የውጭ ማስታወቂያ የጥራት ደረጃና ብቃት

ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ ከመሰራጨቱ በፊት በደንቡ የተቀመጡትን ህግጋትና ባለስልጣኑ በስታንዳርድና በመመሪያ ያስቀመጣቸውን መስፈርቶች የሚያሟላ መሆን ይኖርበታል።

### 1.9 የውጭ ማስታወቂያ የቆይታ ጊዜ

1. በመሬት፣ በሕንፃ፣ በንግድ ድርጅት፣ በአጥር ወይም በማናቸውም መሰል አካል ላይ የሚተከል፣ የሚለጠፍ ወይም በማናቸውም መንገድ የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ የቆይታ ጊዜ ማስታወቂያው የተዘጋጀበትን መሳሪያ እና የተጠቀመውን ግብአት መሰረት በማድረግ ይሆናል፥

   ሀ. ለዲጅታል ስክሪን እና አዲስ ቴክኖሎጂ ለሚጠቀሙ እስከ 6 (ስድስት አመት)፣

   ለ. በሙብራት የሚሰሩ ትልልቅና መካከለኛ ቢል ቦርዶች እስከ 4 (አራት አመት)፣

   ሐ. ከመካከለኛ በታች ለሆኑ ቢል ቦርዶች በጨረታ ለተሰጠ 3 (ሶስት አመት)፣

   መ. በግል ይዞታ ለሚሰጥ በየአመቱ ማደስ ከተቻለ ገደብ አይኖረውም፣

   ሠ. የመንግስት ህንፃ እና ሌሎች የውጭ ማስታወቂያ እስከ 2 አመት፣

2. ከአንድ ወቅታዊ ሁነት ጋር በተያያዘ ለአጭር ጊዜ የሚተከል፣ የሚለጠፍ ወይም በማናቸውም መንገድ የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ ወቅታዊ ሁነቱ ከመከናወኑ በፊት ከአንድ ወር በላይ እንዲሁም ወቅታዊ ሁነቱ ከተጠናቀቀ በኋላ ከሰባት ቀናት በላይ መቆየት የለበትም፣ የማጠናቀቂያ ጊዜ ካለቀ የማስታወቂያ አሰራጩ አካል ማስታወቂያውን በማንሳት ቦታውን የማስረከብ ኃላፊነት አለበት፣

3. በዚህ አንቀፅ 10(2) የተደነገገው ድንጋጌ ለትርፍ ያልተቋቋመ የመንግስት መሥሪያ ቤት በሚያሰራጨው የሕዝብ ማስታወቂያ ላይ ተፈፃሚ አይሆንም።

### 1.10 የምርጫ ውድድር ማስታወቂያ የቆይታ ጊዜ

አግባብ ባለው ሕግ መሰረት ተመዝግበው የሚንቀሳቀሱ የፖለቲካ ድርጅቶችና የምርጫ ዕጩ ተወዳዳሪዎች በምርጫ ወቅት የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ መንገዶችን በመጠቀም የምርጫ ውድድር ማስታወቂያ ማሰራጨት ይችላሉ፣

በዚህ አንቀፅ 11(1) መሰረት የሚሰራጭ የምርጫ ውድድር የውጭ ማስታወቂያ፣

   ሀ) የቆይታ ጊዜው በሚመለከተው አካል በምርጫ ወቅት የሚወሰነው የምርጫ የቆይታ ጊዜ ይሆናል፣

ለ) የተወሰነው የምርጫ ቆይታ ጊዜ በተጠናቀቀ በ30 ቀናት ውስጥ ማስታወቂያው መነሳት ይኖርበታል፣

ሐ) ማስታወቂያው ሌሎች ሕጎችንና የምርጫ ሕግን አክብሮ መሰራጨት ይኖርበታል።

### 1.11 የአገልግሎት ክፍያ እና የሚከፈልበት ጊዜ

1. የውጭ ማስታወቂያ በማናቸውም መንገድ ከመሰራጨቱ በፊት ለፈቃድ ሰጪው የአገልግሎት ክፍያ መከፈል አለበት፣
2. የአገልግሎት ክፍያ ተመን የውጭ ማስተዋወቅ ሥራ የአገልግሎት ክፍያ ለማስከፈል በወጣው ደንብ ቁጥር 117/2013 እና ደንቡን ተከትሎ በሚደረጉ ማሻሻያ መሠረት የሚፈጸም ይሆናል፣
3. በፈቃድ ወቅት ለአገልግሎት ክፍያ የተተመኑትን ክፍያዎች መሰብሰብ የፈቃድ ሰጪው ኃላፊነት ይሆናል፣
4. በምስልና በፅሁፍ የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ የክፍያ ተመን በማስታወቂያ ሰሌዳው ስፋት በሜትር ካሬና በቆይታ ጊዜው የሚሰላ ሲሆን፣ በድምፅ የሚተዋወቅ የውጭ ማስታወቂያ በሚወስደው ጊዜ (በቀን ብዛት) የሚሰላ ይሆናል
5. የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ የተሰጠው ሰው ዓመቱን ጠብቆ የአገልግሎት እድሳት ማድረግ ይኖርበታል።

### 1.12 ከአገልግሎት ክፍያ ነጻ ስለመሆን

1. የሃይማኖት ተቋማት፣ የፖለቲካ ድርጅቶች፣ ለትርፍ ያልተቋቋሙ መንግስታዊ ያልሆኑ ድርጅቶች የዲፕሎማቲክ መስሪያ ቤቶች፣ ዓለም አቀፍ ድርጅቶች፣ ለእምነት ወይም ለዓላማ ማስፈጸሚያ እንዲውሉ በተፈቀዱላቸው ቦታዎች ወይም ንብረቶች ላይ የማስተዋወቅ ሥራ ቢያካሂዱ ከአገልግሎት ክፍያ ነጻ ናቸው፣
2. የፖለቲካ ድርጅቶች፣ መንግስታዊ ድርጅት፣ ለትርፍ ያልተቋቋሙ መንግስታዊ ያልሆኑ ድርጅቶች፣ ዓለም አቀፍ ድርጅቶች፣ ወይም የበጎ አድራጎት ድርጅቶችና የመሳሰሉት ለአላማ ማስፈጸሚያ እንዲያውሉ ከተፈቀዱላቸው ቦታዎች ወይም ንብረቶች ውጭ የውጭ ማስተዋወቅ ሥራ ለማካሄድ ሲጠይቁ፥

   ሀ) በህግ መሠረት ተመዝግቦ የሚንቀሳቀስ የፖለቲካ ድርጅት ከሆነ በምርጫ ወቅት ምርጫን ለመወዳደር፣ የስብሰባ ጥሪ እና መሰል ማስታወቂያዎች ለማሰራጨት፤

   ለ) መንግስታዊ ድርጅቶች ወይም ለትርፍ ያልተቋቋሙ መንግስታዊ ያልሆኑ ድርጅቶች ወይም የበጎ አድራጎት ድርጅቶች ለህብረተሰቡ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ፋይዳ ያላቸው ማስታወቂያዎች ለማሰራጨት፣

   ሐ) ዓለም አቀፍና አህጉራዊ ድርጅቶች ለህበረተሰቡ ወይም አለም አቀፋዊና አህጉራዊ ህብረትን ወይም ግንኙነት ለማጠናከር የሚውል የውጭ ማስታወቂያ ለማስተላለፍ ሲፈልጉ ለአጭር ጊዜ ባለስልጣኑን በማስፈቀድ ከአገልግሎት ክፍያ ነጻ ይሆናሉ፤
3. በበጎ ፈቃደኝነት አካባቢዉን ያለማ ድርጅት ወይም ግለሰብ ባለማዉ አካባቢ ያለማውን መንከባከብ እንዳለ ሆኖ ስለ ድርጅቱ ወይም ሥራዉ የውጭ ማስተዋወቂያ የማሰራጨት ፈቃድ አውጥቶ ከከተማ ውበትና አረንጓዴ ልማት ቢሮ ጋር በሚያደርገው የውል ስምምነት የጊዜ ገደብ ድረስ ሲያሰራጭ ከክፍያ ነጻ ይሆናል፤ በዚሁ መሠረት፡-

   ሀ) በበጎ ፈቃደኝነት ያለማው ሰው ቦታው ላይ ሌላ ሰው እሱን ተክቶ ማስታወቂያ እንዲሰራጭ ሊወክል ወይም አሳልፎ ሊሰጥ አይችልም። ድርጅቱን ወይም ስራውን ለማስተዋወቅ የሚጠቀምበት ሰሌዳ ከሁለት ካሬ ሜትር መብለጥ የለበትም

   ለ) የግንባታ፣ የውሃ የኤሌክትሪክ፣ የቀለምና መሰል ስራ ተቋራጮችና አማካሪዎች ግንባታው በሚከናወንበት ሕንፃ፣ ቦታ ወይም መሳሪያ ላይ ስማቸውንና ስራቸውን ለማስተዋወቅ የሚያስቀምጡት የውጭ ማስታወቂያ፣

   ሐ) በባለሥልጣኑ ከአገልግሎት ክፍያ ነፃ እንዲሆኑ የተወሰነለት ሰው የሚያሰራጨው የውጭ ማስታወቂያ ከክፍያ ነፃ ይሆናል

### 1.13 የአገልግሎት ክፍያ ስለመክፈል

የዚህ መመሪያ አንቀጽ 16 ድንጋጌ ቢኖርም ድርጅቶቹ ለዓላማ ማስፈጸሚያ ባልተፈቀዱላቸው ይዞታዎች ወይም ንብረቶች ላይ የውጭ ማስታወቂያ ሥራ ቢያካሂዱ የአገልግሎት ክፍያ የመክፈል ግዴታ አለባቸው

**1.14 የክፍያ ውሳኔ ማሳወቂያና ክስ አቀራረብ**

1. ፈቃድ ሰጪው የአገልግሎት ክፍያውን ላልከፈለ ሰው የአገልግሎት ክፍያ ውሳኔ ማሳወቂያ እንዲደርሰው ማድረግ ይኖርበታል፣
2. በፈቃድ ሰጪው በደረሰው የአገልግሎት ክፍያ ውሳኔ ማሳወቂያ መሰረት የውሳኔ ማሳወቂያ በደረሰው በ30 ቀናት ውስጥ የሚፈለግበትን ክፍያ አጠቃሎ ያልከፈለ ወይም በ10 ቀናት ውስጥ ለባለስልጣኑ ቅሬታ ያላቀረበ ሰው ማስታወቂያው እንዲነሳ በማድረግ የአገልግሎት ክፍያውንና ማስታወቂያውን ለማንሳት ያወጣውን ወጪ ስልጣን ላለው ፍርድ ቤት አቅርቦ መጠየቅ ይችላል፣

## ክፍል ስድስት

## የማስታወቂያ አስነጋሪ፣ አዘጋጅና አሠራጭ ግዴታና ኃላፊነት

**1.15 ስለ የውጭ ማስታወቂያ ሥራ ግዴታ**

1. ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ አሰራጭ ወይም የራሱን ምርት፣ አገልግሎት ወይም ድርጅት በውጭ ማስታወቂያ በማናቸውም መንገድ እንዲሰራጭ በማስታወቂያ አስነጋሪው የቀረበለትን መረጃ ትክክለኛነት የማረጋገጥ ግዴታ አለበት፣
2. የሚሰራጨው የውጭ ማስታወቂያ በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ (1) በተደነገገው መሠረት ሥነ-ምግባርን የሚጻረር ይዘት ወይም አቀራረብ የሌለው መሆኑን ባለሥልጣኑ ያዘጋጀውን የግዴታ ቅጽ በመፈረም ያረጋግጣል።

**1.16 ስለ ውጭ ማስታወቂያ ሪከርድ ወይም ቅጂ**

ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ አዘጋጅ አሰራጭ ወይም አስነጋሪ፡-

1. የአንድን የተተከለ፣ የተለጠፈ ወይም በማናቸውም መንገድ የተሰራጨ የውጭ ማስታወቂያን ቅጅ ወይም ሪኮርድ ቢያንስ ለ6 ወራት ይዞ ማቆየት አለበት፣
2. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ (1) መሠረት የተያዘውን የማስታወቂያ ሪኮርድ ቅጅና መረጃ ከዚህ መመሪያ አፈጻጸም ጋር በተያያዘ ምክንያት አግባብ ያለው የመንግሥት አካል እንዲቀርብለት ሲጠይቅ በራሱ ወጭ ማቅረብ አለበት።

**1.17 ቁጥጥር እንዲደረግ ስለመፍቀድ**

ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ አሰራጭ ወይም አስነጋሪ በአዋጁ፣ በደንቡና በዚህ መመሪያ መሰረት ለሚደረግ ቁጥጥር የአገልግሎት መስጫ ድርጅቱን ክፍት ማድረግና የሚጠየቀውን ሰነድ የማቅረብ ግዴታ አለበት

**1.18 የውጭ ማስታወቂያ አሰራጭ እና አስነጋሪ ኃላፊነት**

የደንቡንና የዚህ መመሪያ ድንጋጌን በመተላለፍ የተሰራጨ ማስታወቂያ በውጭ ማስታወቂያ ሥራ አዘጋጅ እና አሰራጩ ፈቃድ እንደተሰራጨ ተቆጥሮ እንደ ኃላፊነታቸው መጠን በአንድነት ወይም በነጠላ ተጠያቂ ይሆናሉ።

## ክፍል ሰባት

## በቅንጅትና በትብብር ስለመስራት

**1.19 በቅንጅት ስለመሥራት**

1. ይህን መመሪያና ደንቡን ለማስፈጸም ባለሥልጣኑ ከአዲስ አበባ ከተማ አስተዳር የመሬት ልማትና አስተዳደር ቢሮ፣ መንገዶች ባለስልጣን፡ የኮሚኒኬሽን ቢሮ፣ ደንብ ማከበር ባለሥልጣን እና አካባቢ ጥበቃ ባለሥልጣን ጋር በቅንጅትና በትብብር የመስራት ኃላፊነት አላባቸው፣
2. በዚህ አንቀጽ 27(1) የተጠቀሱት አስፈጻሚ አካላት ለውጭ ማስታወቂያ መትከያ ቦታዎች ዝግጅት፣ ለይዘትና አቀራረብ ቁጥጥር እና እርምጃ አወሳሰድ በሕግ በተሰጣቸው ተግባርና ኃላፊነትን ማከናወን ይኖርባቸዋል፣

3. በዚህ አንቀጽ 27(1) ከተገለጹት አስፈጻሚ አካላት በተጨማሪ ለቅንጅት ስራው አስፈላጊ መሆኑ በባለሥልጣኑ ሲጠየቅ በትብብር ጥምረቱ ውስጥ በጋራ ይሰራል፣

4. የቅንጅት ስራውን የሚያስተባብር ባለሥልጣኑ ይሆናል።

## ክፍል ስምንት

## /ስለ ውጭ ማስታወቂያ ስታንዳርድ/

### የማስታወቂያ አይነቶች

የውጭ ማስታወቂያ ዓይነቶች በሁለት ምድቦች ይከፈላል። እነሱም ቋሚ (fixed) እና ተንቀሳቃሽ (mobile) ናቸው።

**1. የማይንቀሳቀሱ ወይንም ቋሚ (Fixed) የውጭ ማስታወቂያ አይነቶች**

ሀ. ቢልቦርዶች፣ ባነሮች፣ ዲጂታል/ ኤሌክትሮኒክስ ስክሪኖች፣

ለ. የማስታወቂያ ሰሌዳዎች፣

ሐ. በህንፃ ላይ የሚለጠፉ፣

መ. ጣሪያ ላይ የሚሰቀሉና ሌሎችም

**2. የሚንቀሳቀሱ /Mobile Signs/ የውጭ ማስታወቂያ አይነቶች**

ሀ. በመኪና ወይም በተሽከርካሪ ነገሮች ላይ የሚሰራጭ ማስታወቂያ፤

ለ. በተጎታች መረጃ የሚያስተላልፉ ሆነው አስፈላጊ በሆነ ቦታ ላይ ጎትቶ በመውሰድ በማስቀመጥ የሚሰራጭ የማስታወቂያ፤

ሐ. በአየር ላይ የሚንሳፈፍ ፊኛና መሰል ነገሮች ላይ የሚሰራጭ ማስታወቂያ፤

መ. በድምፅ ካሴት መሳሪያ የሚሰራጩ ማስታወቂያዎች፤

**1.20 የውጭ ማስታወቂያ የሚከለከልባቸዉ ቦታዎች**

የትምህርት ተቋማት፣ የጤና ተቋማት፣ የሀይማኖት ተቋማት፣ የመንግስት ተቋማት፣ ኤምባሲዎች፤ አለም ዓቀፍ ድርጅቶች፣ ቤተመንግስት እና የመሳሰሉት ተቋማት አካባቢ ምንም አይነት የውጭ ማስታወቂያ መለጠፍ መስቀል እና ማንጠልጠል የተከለከለ ነው።

**1.21 ስታንዳርዶች እና ማስፈፀሚያ ስልቶች**

የዉጭ የማስታወቂያ መለጠፊያዎችን ወጥነት ባለዉ መልኩ ደረጃዉን የጠበቀ፣ በቴክኖሎጂ የተደገፈ፣ ግልጽ ቀልጣፋና ወጪ ቆጣቢ እንዲሁም ለከተማዋ ተጨማሪ ዉበትን በሚያላብስ መልኩ አገልግሎት እንዲሰጡ ለማድረግ በዚህ ስታዳርድ የታቀዱ የውጭ ማስታወቂያ መለጠፊያ አይነቶች በሚዘጋጁበት ወቅት ሊያሟሉ የሚገባቸዉን ዝርዝር መስፈርቶች (Guide line & Standards) ከዚህ ቀጥሎ በቀረበዉ መልኩ ተዘጋጅቷል።

**1.22 አጠቃላይ ዋና ዋና ስታንዳርዶች**

1.22.1 ማንኛውም የማስታወቂያ ሰሌዳ በሚተከልበት ወይም በሚገነባበት ቦታ በቂ የፀሐይ ብርሃንና መተላለፊያ ያለው፣ የእግረኛና የተሽከርካሪ እንቅስቃሴ የማይከለክል፣ የማያውክ፣ የማይገድብ እና ነጻ መሆን አለበት፣

1.22.2 ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ አስነጋሪ ድርጅት/ተቋም/ በአንድ በቦታ ላይ በተሰጠው ፍቃድ ሌላ አከባቢ/ቦታ/ መትከል አይቻልም፣

1.22.3 ማንኛውም የውጭ ማስታወቂያ ከተሰቀለበት ሰሌዳ ወርድና ቁመት መትረፍ የለበትም፣

1.22.4 ለፈቃድ የሚቀርቡ የውጭ ማስታወቂያ ይዘቶች በሀገሪቱ የስራ ቋንቋ መቅረብ አለባቸው፣

1.22.5 የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳ መጠኖች በሜትሪክ ሲስተምና በግራፊክ ስታንዳርድ መቅረብ አለባቸው፣

1.22.6 የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳ በመስታወት የሚሰራ ከሆነ የመስታወቱ ውፍረት 6 ሚሊ ሜትር ሆኖ ቢሰበርም የማይረግፍ መሆን አለበት፣

1.22.7 በኤሌክትሪክ የሚሰሩ ዲጂታልና ባለብርሀን ማስታወቂያ ሳጥን /Light box/ የራሱ የኤሌክትሪክ መስመርና መቆጣጠሪያ ያለው መሆን አለበት፣

1.22.8 የመሰረተ ልማት አውታሮችን በማይጎዳና አግባብ ባለው አካል የተዘጋጀ የስትራክቸራል ውቅር ንድፍ በሚያቀርበውና በሚያዘው መስፈርት መሰረት ይወሰናል፣

1.22.9 የወረቀትና ወረቀት ነክ ማስታወቂያ መለጠፊያ ቦርዶች ላይ ብቻ ካልሆነ በስተቀር በሌላ ቦታ ምንም አይነት ማስታወቂያ መለጠፍ አይቻልም፣

1.22.10 በመኪና፣ በባቡር እና በእግረኛ መሸጋገሪያ ድልድይ ምሰሶዎች ላይ ምንም አይነት የውጭ ማስታወቂያዎች መስቀል የተከለከለ ነው፣ ነገር ግን በድልድዮች ላይ መስቀል ይቻላል፣

1.22.11 ውበቱ ሲጓደልና የውል ጊዜው ሲያልፍ በጨረታው ያሸነፈው ድርጅት ውሉን ካጠናቀቀ በኋላ ማስታወቂያውን አንስቶ ላዋዋለው አካል ማስረከብ አለበት፣

1.22.12 በማንኛውም ዘዴ የሚሰራጩ የውጭ ማስታወቂያዎች ከይዘት አኳያ ማናቸውንም ሕግ ወይንም መልካም ስነ ምግባር የማይፃረር፣ አሳሳች ወይንም ተገቢ ካልሆነ አገላለፅ ነፃ የሆነ፣ የህብረተሰቡን ማህበራዊና ባህላዊ እሴት የሚያከብርና የሸማቹን ህጋዊ ጥቅም የማይጎዳ፣ የሚተዋወቀውን ምርት ወይንም አገልግሎት እውነተኛ ባህሪ፣ ጥቅም፣ ጥራትና መሰል መረጃዎችን የሚገልፅ ፣ የሌሎችን ሰዎች ምርት ወይንም አገልግሎት የማያንቋሽሽ፣ የአገርን ክብርና ጥቅም የሚጠብቅ እና የሙያ ስነምግባርን የሚያከብር ይዘትና አቀራረብ ያለው መሆን አለበት።

1.22.13 በህንጻ የውጭ መስታወት በር፣ መስኮት እና የግንባታ ማጠናቂያ ቁሶች ላይ ምንም አይነት የውጭ ማስታወቂያ ማስተላለፍ አይቻልም፣ ሆኖም ግን በህንፃ ውስጥ ባሉ የፓርቲሽን መስታወት በር፣ መስኮት እና የግንባታ ማጠናቂያ ቁሶች ላይ በአከፋፈል ደንብ ቁጥር 117/2013 መሰረት በማስከፈል መፈቀድ ይቻላል፣

1.22.14 በድምፅ ማጉያ መሳሪያ ወይም በድምፅ ካሴት በመጠቀም ምርትንና አገልግሎትን ለማስተዋወቅ ግለሰቡ ወይም ድርጅቱ በአካባቢ ጥበቃ ባለስልጠን በኩል የድምፅ ስታንዳርድ ይሁንታ ሲያገኝ ፈቃድ ይሰጣል፣

1.22.15 የቋንቋ አጠቃቀምን በተመለከተ የማስታወቂያ ፈቃድ አዋጅ ቁጥር 759/2004 አንቀጽ 21/3 የውጭ ማስታወቂያ በአገር ውስጥ ቋንቋ ወይም ፊደል የተጻፈ መሆን ወይም በውጭ ቋንቋ ወይም ፊደል ጭምር የተጻፈ ሲሆን የአገር ውስጥ ቋንቋው ወይም ፊደሉ ከውጭው ቋንቋ ወይም ፊደል አስቀድሞ ወይም ከላይ ሆኖ የተጻፈ መሆን አለበት።

1.22.16 በስፖንሰር የሚቀርቡ የውጭ ማስታወቂያ በ0.3ካ.ሜ. ስፋት የስፖንሰር አድራጊው ስም፣የንግድ ምልክቱ ወይም ሎጎና ለስፖንሰሩ የሚቀርብ ምስጋና ከመግለጽ ውጭ የስፖንሰሩ ምርት ወይም አገልግሎት እንዲሸጥ ወይም እንዲከራይ መተዋወቅ ወይም መቀስቀስ የለበትም።

1.22.17 በአንድ ገጽ በኩል ብቻ የሚሰራ የማስታወቂያ ሰሌዳ ጀርባው የከተማውን ውበት በማያበላሽና ንጹህ በሆነ ቁስ የተሸፈነ መሆን አለበት።

1.22.18 ማንኛውም የማስታወቂያ ሰሌዳ ፈቃድ የተሰጠው ሰው የሰሌዳ መትከያ ቦታውንም ሆነ የሰሌዳውን ንጽሕና የመጠበቅ ግዴታ አለበት።

1.22.19 የሚተከል ወይም የሚገነባ ወይም የሚሰቀል የውጭ ማስታወቂያ የህውልት ወይም ማንኛውንም ቅርስ እይታን የሚጋርድ መሆን የለበትም።

1.22.20 ማንኛውም ማስታወቂያ ብልጭ-ድርግም የሚሉ እንዲሁም የመንገድ ተጠቃሚውን እይታ በሚረብሽ መልኩ የሚያንፀባርቁ መሆን የለባቸውም፡ ነገር ግን በምሽት እንዲነበቡ ተደርገው የብርሀን ብክለት በማያስከትል ሁኔታ መሰራት አለበት።

1.22.21 በማስታወቂያው የታችኛው ጠርዝ ላይ (ምሶሶው ላይ) 0.3 ካሬ ሜትር ባልበለጠ ቦታ የማስታወቂያ ወኪል ስምና አድራሻ፣የፈቃድ ቁጥሩ፣ፈቃዱን የሰጠው አካልና ፈቃዱ የሚያበቃበት ጊዜ ከመሬት ላይ በሚታይ መልኩ መፃፍ አለበት።

### 1.23 በአደባባይ ዙሪያ ባሉ ክፍት ቦታዎች የሚተከሉ የውጭ ማስታወቂያ ቢልቦርዶች

በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ከአንዱ ማስታወቂያ ጠርዝ እስከ ሁለተኛው ማስታወቂያ ጠርዝ ያለው ዝቅተኛው ርቀት ሶስት ሜትር ሊሆን ይገባል። ሶስት ሜትር ላይ ማስታወቂያውን ለማስቀመጥ የማያስችል ነባራዊ ሁኔታ ሲገኝ እስከ አራት ሜትር ድረስ ሊጠበቅ ይችላል ሆኖም ግን ከሶስት ሜትር ርቀት በታች ማስታወቂያዎችን መትከል አይቻልም።

**ማስታወቂያዎች ከሦስት ሜትር በላይ ርቀት እንዲጠብቁ የሚያስገድዱ ሁኔታዎች መካከል፡-**

1.23.1 ለአካባቢ ውበት ተብለው የተተከሉ አጽዋት ማስታወቂያው ሊተከልበት በታሰበበት ቦታ ላይ ሲገኙ፤

1.23.2 ስልጣን ባለው አካል የለሙ ቦታዎች ሲገኙና ቦታው ለማስታወቂያ ሲውል የሚያስከትለው ጉዳት አምዝና ከተገኘ፣

1.23.3 በአካባቢው ላይ በመንግስት ወጪ ለልማት ተብለው የተገነቡ መሰረተ ልማት አውታሮች ካሉ

**ለምሳሌ፥** የቆሻሻ መጣያ፣ የመንገድ ዳር ምሰሶዎች



1.23.4 በዋና ዋና መንገድ አደባባይ ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ከእግረኛ መንገድ ጠርዝ አንድ ሜትር እንዲርቁ ይደረጋል።

1.23.5 በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች እንደ አስፈላጊነቱ ከ6 ሜትር ወርድ ስፋት በላይ ያልሆኑ ማስታወቂያዎች መተከል አለባቸው።

1.23.6 በአደባባይ መሃል ምንም ዓይነት ማስታወቂያ ሰሌዳ መትከል፣ መለጠፍ ወይም ማንጠልጠል አይቻልም ሆኖም አደባባዮችን የሚያለማ ባለሀብት ምርቱንና አገለግሎቱን ለማስተዋወቅ የሚፈቀደው አደባባዩ በሚፈቀድለት ቴክኒካል መስፈርት ወይም ስታንዳርድ መሰረት ቅርጻ ቅርጾችን፣ ሀውልቶችን፣ ፋውንቴኖችን እና ሰው ሰራሽ ወንዞችን መገንባት ይችላል። እንዲሁም የሚያለማ ባለሀብት የማስተዋወቅ ስራ ለማከናወን በአደባባይ ዙሪያ ከ2 ካ.ሜትር ያልበለጠ ስሌዳ መጠቀም ይችላል።

1.23.7 በአደባባይ ላይ የሚሰቀሉ ተከታታይ ማስታወቂያዎች እስከ 6 ሜትር ወረድ ያልበለጡየውች ማስታወቂያዎች የሚተከሉ ቢሆንም አንዱ ማስታወቂያ ከሌላው ማስታወቂያ ቢቻል በተመሳሳይ ምጣኔ ማለትም ወርድ እና ቁመት ካልሆነ ግን አንዱን ምጣኔ እንዲጠብቅ ይደረጋል ይህም የእይታ ወጥነትን እንዲፈጠር ታሳቢ የተደረገ ነው፣

1.23.8 በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች የቦታ ተደፋት ልዩነት (Slope) ልዩነት ሲኖራቸው ጎን ለጎን የሚተከሉ ማስታወቂያዎችን ቁመት ለማስታረቅ እንደ አስፈላጊነቱ የቋሚ ቁመት ከ2.5 ሜትር ሊበልጥ ይችላል፣

1.23.9 በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ማህበራዊ ኃላፊነትን ለመወጣት የሚያስችል አንድ ክንውን ከማስታወቂያው ጎን ለጎን ማካተት ይጠበቅባቸዋል፣

1.23.10 ለምሳሌ፡- ቆሻሻ መጣያ ፣ የሊስትሮ መቀመጫ ቦታዎችን

1.23.11 በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች አንደኛውን ገጽ ለማየት አዳጋች የሆነ ሁኔታ ከሌለ የማስታወቂያ ቦታዎችን ብክነት እና ምጣኔያዊ አጠቃቀም ለመጠበቅ ሲባል በሁለቱም (ገጽታ) በኩል ማስታወቂያዎችን እንዲሰቀል ይዳረጋል።

1.23.12 በአደባባይ ዙሪያ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች በሁለት ተከታታይ የማስታወቂያ ሰሌዳዎች መካከል ያለው ርቀት ቢያንስ 3 ሜትር መሆን አለበት

**1.24 በዋና ዋና እና መጋቢ መንገዶች ላይ የሚተከል የውጭ ማስታወቂያ መስፈርቶች**

**ከ25 ሜትር ስፋት እና በላይ (PAS፣ SAS እና RR)**

1.24.1 በዋና ዋና መንገዶች ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ለዋና ዋና መንገዶች ተብለው የተጠቀሱትን የማስታወቂያ ልኬት አማራጮች በመውሰድ በ50 ሜትር ርቀት ውስጥ የሚተከሉ ይሆናል።

1.24.2 ሆኖም በ50 ሜትር ርቀት ውስጥ ማስታወቂያ ለመትከል የማያስችል ሁኔታ ቢገኝ፣

**ለምሳሌ፡-** የማስታወቂያው በስተጀርባ የሚከለል ህንፃ ቢኖር፣ ኢምባሲ ቢኖር፣ የህዝብ መገልገያ ፓርክ ቢኖር ከ 50 ሜትር ሳያንስ ክፍት ቦታ እስኪገኝ የሚቀጥል ይሆናል፣

1.24.3 በዋና ዋና መንገዶች ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች የእግረኛንም ሆነ የአሽከርካሪን እይታ በማይጋርድ ከ2.5 ሜትር ከፍታ ላይ መተከል ይኖርባቸዋል፣

1.24.4 ማንኛውም በከተማዋ ዋና ዋና መንገዶች ላይ የሚገኙ ክፍት ቦታዎች ላይ ከሚመ"ለከተው አካል ተገቢውን አዎንታ ሳያገኙ ማስታወቂያ መትከል በተጠቀሰው የውጭ ማስታወቂያ በመመሪያ 117/2013 ደንብ መሰረት ቅጣቱ ተፈፃሚ ይሆናል፣

1.24.5 በዋና ዋና መንገዶች ላይ መስቀለኛ አቋራጮች ሲገኑ ከእያንዳንዱ የመንገዱ ጠርዝ 12 ሜትር ርቀት ድረስ ማስታወቂያ መትከል አይቻልም፣

1.24.6 ዋና ዋና መንገዶች ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ማስታወቂያውን ለመትከል በቂ ያልሆነ ቦታ ከሆነ ለመንገዱ ትይዩ እንዲሆን ይገደዳል፣

1.24.7 ሆኖም በቂ ቦታ ከተገኘ የእግረኛን እንቅስቃሴ በማያውክ መልኩ ለእግረኛው ትይዩ (ፊት ለፊት) በሆነ አቅጣጫ ከ2.5 ሜትር ከፍታ ላይ የእግረኛን እንቅስቃሴ በማያውክ መልኩ ሊተከል ይችላል፣





6.0 ሜትር * 3.0 ሜትር

የመንገድ ቅርጻቸው ከሁለት አቅጣጫ እይታን በሚፈቅዱ ቦታዎች ላይ ሁለት ማስታወቂያዎችን ለእይታ በተመጠነ አንግል ሊቀመጡ ይችላሉ፣




የመንገድ ቅርጻቸው ከሶስት አቅጣጫ እይታን በሚፈቅዱ ቦታዎች ላይ ሶስት ማስታወቂያዎችን ለእይታ በተመጠነ አንግል ሊቀመጡ ይችላሉ፣



6 ሜትር * 6 ሜትር

5 ሜትር * 5 ሜትር






3.5 ሜትር * 6 ሜትር

2.5 ሜትር * 4 ሜትር

**1.25 መጋቢ መንገዶች ላይ የሚተከል የውጭ ማስታወቂያ መስፈርቶች**

**15-20 ሜትር ስፋት (Collecter Road)**

1.25.1 በሁለት ተከታታይ የማስታወቂያ ሰሌዳዎች መካከል ያለው ርቀት ቢያንስ /ሃምሳ/ ሜትር መሆን አለበት፣

1.25.2 በማስታወቂያ ምሰሶው ላይ 0.3 ካሬ ሜትር ባልበለጠ ቦታ ላይ የማስታወቂያ ወኪሉ ስምና አድራሻ፣ የፈቃድ ቁጥሩ፣ ፈቃዱን የሰጠው አካልና ፈቃዱ የሚያበቃበት ጊዜ በሚታይ መልኩ መፃፍ ሲኖርበት፤ የማስታወቂያ ፈቃድ ባለቤቱ መረጃው ተሟልቶ መቀመጡን ይከታተላል፣




**1.26 በውስጥ ለውስጥ መንገድ የሚተከል የውጭ ማስታወቂያ ቢልቦርድ**

**ከ10 ሜትር ስፋት እና ከዚያ በታች (local streat)**

1.26.1 በማስታወቂያ ምሰሶው ላይ 0.3 ካሬ ሜትር ባልበለጠ ቦታ ላይ የማስታወቂያ ወኪሉ ስምና አድራሻ፣ የፈቃድ ቁጥሩ፣ ፈቃዱን የሰጠው አካልና ፈቃዱ የሚያበቃበት ጊዜ በሚታይ መልኩ መፃፍ ሲኖርበት ፤ የማስታወቂያ ፈቃድ ባለቤቱ መረጃው ተሟልቶ መቀመጡን ይከታተላል።

**ባለአንድ ገጽ ከሆነ፤**

- ቋሚው ከመሬት በላይ ያለው ከፍታ በያንስ 2.50 ሜትር በላይ መሆን አለበት።
- በሁለት ተከታታይ የማስታወቂያ ሰሌዳዎች መካከል ያለው ርቀት ቢያንስ 2 ሜትር መሆን አለበት።

**ባለ ሁለት ገጽ ማስታወቂያ ሰሌዳ ከሆነ**

- ጥያቄው በሚቀርብበት ጊዜ ቦታው የሚያመች መሆኑ በፈቃድ ሰጪው አካል አስተያየት መረጋገጥ አለበት፤ በፈቃድ ሰጪው አካል አስተያየት ቦታው የሚያመች ሆኖ ከተገኘ ባለሁለት ገጽ የማስታወቂያ ሰሌዳ መትከል የሚቻል ሲሆን ፤
- ቋሚው ከመሬት ያለው ከፍታ ከ2.5 ሜትር በላይ መሆን አለበት።
- ሁለት ተከታታይ የማስታወቂያ ሰሌዳዎች መካከል ያለው ርቀት ቢያንስ 10 ሜትር መሆን አለበት።

0.4ሜትር*0.7ሜትር
0.5ሜትር*0.8ሜትር
0.6ሜትር*0.1ሜትር



1.8ሜትር*1.4ሜትር
1.4ሜትር*0.8ሜትር



**1.27 መካከለኛ የውጭ የማስታወቂያ መለጠፊያ ሠሌዳ**

ይህ የማስታወቂያ መለጠፊያ በሰዉ ቁመት ሊነበብ የሚችሉ የማስታወቂያ አይነቶችን የሚይዝ ሲሆን የማስታወቂያወቹ ሰሌዳ አይነትም በህትመት የሚለጠፉ (Hard Copy Display) ወይንም ዲጂታል ስክሪን ላይ የሚተላለፉ ሊሆን

ይችላል። በዲጅታል ስክሪን የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች ማስታወቂያዉ ከሚሰራጭበት ጣቢያ ጋር በገመድ አልባ ኔትዎርክ አማካኝነት በማገናኘት የሚተላለፍ ይሆናል። ይሁን እንጅ የሁለቱም የሰሌዳ አይነቶች ከዚህ ቀጥሎ በተዘረዘረዉ ስታንዳርድና መመሪያ መሰረት የሚዘጋጁ ይሆናል።

- ✓ የማስታወቂያ ሰሌዳዉ የሚቀመጥበትን ቦታ ከግምት ዉስጥ በማስገባት
  - ባለአንድ ወይም ባለሁለት ገጽ ሊሆን ይችላል
  - ከሚኖረዉ ተጠቃሚ የህብረተሰብ ብዛት አንፃር እስከ ሁለት የማስታወቂያ ሰሌዳዎች ጎን ለጎን ሊገነቡ የሚችሉ ሲሆን በሁለት ማስታወቂያዎች መካከል ቢያንስ የ1ሜትር ክፍተት መሆን ይኖርበታል።
- ✓ ይህ የማስታወቂያ መለጠፊያ አይነት ሶስት ክፍሎች የሚኖሩት ሲሆን እያንዳንዳቸዉም የተለያዩ የማስታወቂያ ሁኔታዎችን (የአገልግሎት ሰጪ፣ የጨረታ፣ ማሳሰቢያና የስራ ማስታወቂያዎችን) የሚይዝ ሲሆን ከ5ካ.ሜ ያነሰና **ከ6ካ.ሜ** በላይ መሸፈን የለበትም (Maximum permitted Area = 6m2).




- ✓ የማስታወቂያ ሠሌዳው ቁመት 125 ሳ.ሜ እና ወርዱ 225 ሳ.ሜ
- ✓ ከመሬት የሚኖረዉ ከፍታ 90 ሳ.ሜ
- ✓ የግንባታ ግብአት
  - ግብአት (Material)፡ የማይዝግ ብረት (ስቴንለስ ስቲል)
  - ቋሚ ምሰሶ /Post/፡ ብዛት 4 መጠን (10*15 ሳ.ሜ)
  - ቋሚ ምሰሶዉ ከምድር ጋር በብሎን የሚታሰር ይሆናል።
- ✓ **መስታወት**፡ ቀለም የሌለዉ 100% ብርሀን አስተላላፊ ፖሊካርቦኔት ወይም የማይረግፍ መስታወት መሆን አለበት
- ✓ ከፋይበር መስታዉት የሚሰራ 100ሳ.ሜ ስፋት ያለዉ የዝናብና የፀሀይ ነፀብራቅ መከላከያ አብሮ የሚሰራ ይሆናል።
- ✓ የማስታወቂያ መለጠፊያዉ በር ፍሬም ባለ 10ሳ.ሜ

- ማጠፊያ ከላይ ሆኖ ወጥ በር የሚዘጋጅ ሲሆን በሩም ወደላይ ተከፋች ይሆናል
- የበሩ ድጋፍም ባለ ተንቀሳቃሽ ስፕሪንግ ይሆናል

✓ **መብራት፡** ከማስታወቂያ መለጠፊያዉ ላይ የሚቀመጡት የLED መብራቶች ሲሆኑ አንባቢዉን በቀላሉ ወደሚፈልገዉ የመረጃ አይነት የሚመሩ የማስታወቂያ አይነቶችን አርዕስት የሚያመላክት ፅሁፎች የሚይዝ ይሆናል።

✓ የአንባቢዉን ምቾት (Comfort) ለመጠበቅ ያስቻላል ዘንድ የማስታወቂያ ሰሌዳዉ አቀማመጥ የፀሀይን እንቅስቃሴን (Sun Orientation) ታሳቢ ሊያደርግ ይገባል።

የጎን እይታ (Side Elevation)







## 1.28 የተቀናጀ የማስታወቂያ ቦርድ

ይህ የቦርድ ማስታወቂያ አይነት መካከለኛ ቢል ቦርድን ከመካከለኛ የማስታወቂያ መለጠፊያ ሰሌዳ ጋር ተቀናጅቶ የሚዘጋጅ ሲሆን ከስር የሚገነባዉ ለመካከለኛ የማስታወቂያ ሰሌዳ ተብሎ በተቀመጠዉ ስታንዳርድ መሰረት የሚገነባ ሲሆን ከላይ ተቀናጅቶ የሚገነባዉ የመካከለኛ ቢል ቦርድ የማስታወቂያ መለጠፊያ ከዚህ ቀጥሎ የተቀመጡትን መስፈርቶች ማሟላት ይኖርበታል፤

ይህ የማስታወቂያ መለጠፊያ ቦርድ የታተሙ ማስታወቂያዎችን ወይንም በዲጂታል ስክሪን የሚዘጋጅ ይሆናል፤

1.28.1 ወርዱ ከመካከለኛ ቢል ቦርድ የማስታወቂያ መለጠፊያ ወርድ (225ሳ.ሜ) ጋር እኩል መሆን ያለበት ሲሆን ቁመቱ ደግሞ ከ225ሳ.ሜ መብለጥ የለበትም፤

1.28.2 በተተከለበት መሬትና በማስታወቂያው የታችኛው ጠርዝ መካከል የሚኖረው ከፍታ ከ305 ሳ.ሜ ማነስ እና ከመሬት የሚኖረው አጠቃላይ ከፍታ 530 ሳ.ሜ ሙብለጥ የለበትም፣

1.28.3 ከላይ የሚገነባዉ የመካከለኛ ቢልቦርድ የማስታወቂያ ሰሌዳ እንደሚኖረን ሶስት አይት አቀማመጥ (ትይዩ፣ የመንታ መጋጠሚያ /V Shape/ እና ባለ ሦስት ገፅ) ሊኖረዉ ይችላል፣ ከእነኚህ ዉስጥ በባለ ሦስት ገጽ የሚዘጋጅ የተቀናጀ የማስታወቂያ ቦርድ በሶስቱም አቅጣጫ ማስታወቂያዎችን ለማስተላለፍ የሚያስችል መሆን አለበት፤

1.28.4 ራሱን ችሎ መሀከል ላይ የሚቆም በመሆኑ ከሌሎች የማስታወቂያ ሰሌዳዎች አቀማመጥ አንፃር ትልቅ ቦታ (ከ15ካ.ሜ ያላነሰ ቦታ) ይፈልጋል። በመሆኑም የሚዘጋጀዉ ዲዛይን የሚኖረዉን የቦታ ስፋትና አስፈላጊነቱን ከግምት ዉስጥ ማስገባት ይኖርበታል።




**1.29 በመንገዶች ዳርቻ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች**

1.29.1 የእግረኛን እንቅስቃሴ የማያውኩ መሆን ይኖርባቸዋል፣

1.29.2 የእግረኛን እንቅስቃሴ ታሳቢ በማድረግ የእግረኛ ፍሰት በማይበዛባቸው ቦታዎች ብቻ መተከል ይኖርባቸዋል፣

1.29.3 በመንገዶች ዳርቻ የሚተከሉ ማስታወቂያ ከኋለኛው እግረኛ መንገድ ጠርዝ ድንጋይ /Back curbe stone/ በኋላ አነስተኛው ርቀት 0. ሜትር መሆን አለበት፣






### 1.30 በህንጻ ላይ የሚሰቀልሉና የሚለጠፉ ማስታወቂያዎች

#### 1.30.1 በህንፃ አናት ወይም ጣሪያ ላይ

- በሕንጻ አናት ወይም ጣሪያ ላይ የሚሰቀል ወይም የሚለጠፍ የውጭ ማስታወቂያ በምንም መልኩ ወደ ጣሪያው ጠርዝ መጠጋት የለበትም።
- የህንጻው ባለቤት የማስታወቂያ ወኪሉን ስምና አድራሻ፣ የፈቃድ ቁጥሩ፣ ፈቃዱን የሰጠው አካልና ፈቃዱ የሚያበቃበት ጊዜ መዝግቦ መያዝ ይኖርበታል።
- የፈቃድ ጊዜው ያለፈበትን ማስታወቂያ እንዲወርድ ወይንም እንዲያሳድስ የማድረግ ኃላፊነት ያለበት ሲሆን ይህን አለማድረጉ በህንፃው ላይ የማስታወቂያ ስራ እንዳያከናውን ከመታገዱም በላይ አስተዳደራዊ መቀጮ ይጣልባቸዋል።




- በሕንጻ አናት ወይም ጣሪያ ላይ የሚሰቀል ወይም የሚተከል የዉጭ ማስታወቂያ ቁመቱ ከ3 ሜትር መብለጥ የለበትም።
- ሆኖም ከዚያ በላይ ጥያቄ ሲቀርብ የአካባቢው የህንጻ ከፍታ ደንብ በጠበቀ መልኩ ሆኖ የህንጻው ውቅር /Structure/ የሚፈቅደው መሆኑ መረጋገጥ አለበት። የህንጻው ውቅር ትንተና /Structural Analysis/ መቅረብ አለበት።

#### 1.30.2 በሕንጻው ግድግዳ ላይ የሚለጠፍ ወይም የሚሰቀል የማስታወቂያ ሰሌዳ፤

- የማስታወቂያ ሰሌዳው የህንፃውን የመስኮት፣ የበር፣ ወይም የአደጋ ጊዜ መውጫን የሚጋርድ መሆን የለበትም፣ በሕንጻው የጎን ገጽ ላይ ከአንድ ማስታወቂያ በላይ መለጠፍ አይቻልም፣
- የሚሰቀለው የማስታወቂያ ሰሌዳ ከሕንጻው ጠርዝ መትረፍ የለበትም፣
- የሚሰቀለው የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳ ሊለጠፍበት ከታሰበው የጎን ግድግዳ ገጽ ብቻ 70% ፐርሰንት መሆን አለበት፣ ነገር ግን የህንጻውን ውበት እና አርክቴክቸራል (Façade) ተከትሎ እና ከሌሎች ህንጻዎች ጋር የተናበበና የማይቃረን መሆን አለበት፤




- የውጭ ማስታወቂው ቀለም ከህንፃው ማቴሪያል ጋር መዋሀድ(Harmonized) እና መልካም እይታ መፍጠር አለበት፣
- የህንጻዉን ዉበት(Façade) ከመጠበቅ አንጻር በህንጻዎች የፊት ለፊት ገጽ ላይ የሚሰቀሉ የውጭ ማስተወቂያዎች፡-
  - ✓ በከተማዋ ከሚገኙ Old city ውስጥ ፒያሳ ላይ በተደረገው የዳሰሳ ጥናት የተሰቀሉ የውጭ ማስተወቂያዎች ቁመታቸው 1 ሜትር ሆኖ የህንፃውን ዉበት (Façade) እና ድግግሞሽ (Rhythm) በጠበቀ መልኩ የተሰሩ በመሆኑ በጥሩ ተሞኩሮ ሊወሰድ በመቻሉ ከዚህ በታች የተዘረዘሩትን ስታንዳርዶች ተዘጋጅተዋል፣




✓ **በህንፃዎች ፊት ለፊት** ላይ የሚሰቀሉ የሚለጠፉና የሚንጠለጠሉ የውጭ ማስታወቂያዎች

- የህንፃው የበረንዳ መደገፊያዎች(Handrail) ላይ እና የህንጻዉ Facade ተከትሎና pattern ጠብቆ በ1ሜትር ቁመት መለጠፍ፣ ማንጠልጠል ወይም መስቀል ይኖርበታል።




### 1.30.3 በህንፃ ላይ ባሉ ገፆች ላይ በፅሁፍ የሚሰቀል ማስታወቂያዎች

- በህንፃ ውጫዊ አካል ላይ ለሚለጠፉ የህንፃውን ስም የሚገልፅ ፅሁፎች መጠናቸው ጉልህ የሆነና በጥራት መታየት አለበት፣
- የእያንዳንዱ ፅሁፍ የቁመት ምጣኔ ከአንድ ሜትር ከሀምሳ ያልበለጠ እና ከሰማንያ ሳንቲ ሜትር ያላነሰ መሆን አለበት፣




### 1.30.4 በሕንጻው ግድግዳ ላይ ወጣ ብሎ የሚሰቀል የማስታወቂያ ሰሌዳ፤

- ይህ የሰሌዳ አይነት ወርዱ ከ80 ሳ.ሜ ያልበለጠ እና ከህንጻው አካል ጋር ያለው ውቅር የጠበቀ እንዲሁም ክብደት ከሌላቸው ቁሶች የሚሰራ በተጨማሪም የእግረኛን እንቅስቃሴ በማያውክ መልኩ ከመሬት ቢያንስ 3 ሜትር ከፍታ ሊኖረው ይገባል፣




### 1.30.5 በህንጻዎች ፊትለፊት የሚቀመጡ ማስታቂያዎች

- የውጭ ማስታወቂያው የሚቀመጡበት ቦታ ከ0.6 ሜትር ስኩዌር የማይበልጥ ሆኖ የማስታወቂያው ቦርዱ ስፋት 1.00 ሜትር x 0.6 ሜትር መብለጥ የለበትም፣

- እነዚህ ማስታወቂያዎች የእግረኛ መንገድ ላይ መቀመጥ አይችሉም፣ ሆኖም በህንፃ እና በእግረኛ መንገድ መካከል ባሉ ክፍት ቦታዎች እና ህንፃው በተዋቸው ክፍተቶች ላይ ብቻ የሚቀመጥ ይሆናል፣




## 1.31 በድልድዮች ላይ የሚሰቀሉ ማስታወቂያዎች

1.31.1 ቁመታቸው ከአንድ ሜትር ከሀያ መብለጥ የለበትም፣

1.31.2 የውጭ ማስታወቂያው ወርዳቸው እንደ ድልድዩ መጠን ቦታ ላይ በማስታወቂያ ፈቃድ ሰጪው አካል የሚወሰን ይሆናል፣

1.31.3 የአሽከርካሪዎችን የእይታ መዘበራረቅ ለመግታት በአንደድ ድልድይ ላይ በአንድ አቅጣጫ ከአንድ በላይ ማስታወቂያ መስቀል አይቻልም፣




## 1.32 አስገዳጅ በሆነና አትክልቱ እስኪያድግ ድረስ አካፋይ መንገዶች ላይ እና የአረንጓዴ ቦታዎች መከለያ ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች

1.32.1 የአጥር ቁመታቸው 0.75 ሜትር መብለጥ የለበትም፣

1.32.2 አካፋይ መንገዶች ላይ እና የአረንጓዴ ቦታዎች ለመከለያ የሚሆን ቦታ ላይ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች በየ20 ሜትር ርቀት መለጠፍ አለበት፣

1.32.3 የአንዱ ማስታወቂያ ስፋት ወርዱ 40 ሳንቲ ሜትር ሆኖ ቁመቱ 60 ሳንቲ ሜትር መሆን አለበት፣




## 1.33 በአጥር ላይ የሚሰቀሉ ማስታወቂያዎች

### 1.33.1 የግለሰቦች አጥር

- ✓ የማስታወቂያ ፍቃድ ወቶበት ለሚለጠፍ ወይም ለሚሰቀል ማስታወቂያ የበሩን ተካፋች ሳይነካ ከቀሪው ድፍን ግድግዳ /solid wall/ ግሪል ያልሆነውን የአጥር ክፍል ላይ ሰማንያ ፐርሰንቱን (80%) ብቻ መሸፈን ይኖርበታል፣

### 1.33.2 የተቋማት አጥር

- ✓ የበሩን ተካፋች ሳይነካ ከቀሪው ድፍን ግድግዳ /solid wall/ ግሪል ያልሆነውን የአጥር ክፍል ላይ ሰማንያ ፐርሰንቱን (80%) ብቻ መሸፈን ይኖርበታል፣
- ✓ ለአካባቢ ልማት የሚለሙ አትክልቶችን በማይነካ መልኩ ከመሬት ሰባ ሳንቲም ከፍታ ላይ መቀመጥ ይኖርበታል፣



### 1.34 በመንገድ ዳር የመቀመጡ የደረቅ ቆሻሻ ማጠራቀሚያ ላይ የሚለጠፉ ማስታወቂያዎች

| | |
|---|---|
| • በመንገድ ዳር በመቀመጡ የደረቅ ቆሻሻ ማጠራቀሚያዎች ላይ የሚለጠፉ ማስታወቂያዎች ለማስታወቂያ ተብሎ በተዘጋጀ ቦታ ላይ ሙሉ ለሙሉ መሸፈን ይኖርበታል፡፡ በተጨማሪም ከሚያስተዳድረው አካል የአዎንታ ደብዳቤ ያስፈልጋል፡፡ | |

### 1.35 በአውቶቢስ እና በባቡር መጠበቂያ ቦታዎችየሚለጠፉ ማስታወቂያዎች

| | |
|---|---|
| • በአውቶቢስ እና በባቡር መጠበቂያ ቦታዎች ላይ ባሉ የተሳፋሪ መቀመጫዎች ላይ የሚሰቀሉ ማስታወቂያዎች ለማስታወቂያ ተብሎ በተዘጋጀ ቦታ ላይ ሙሉ ለሙሉ መሸፈን ይኖርበታል፡፡ በተጨማሪም ከሚያስተዳድረው አካል የአዎንታ ደብዳቤ ሊቀርብላቸው ይገባል፡፡ | |

#### 1.35.1 የአውቶብስ መጠበቂያ መጠለያዎች ላይ የተዘጋጁ የማስታወቂያ ቦታዎች

የማይዝግ ብረት (ስቴንለስ ስቲል) የአውቶብስ መጠበቂ መጠለያዎች ላይ አላማቸው ለማስታወቂያ ማሳያ ተብለው የተሰሩ ባለብርሀን የማስታወቂያ ሳጥኖች (Light Boxes) ሲኖሩ እነዚህም ሁለት አይነት መጠን ያላቸው ናቸው፡፡

**ዓይነት 1**

- ✓ የሳጥን ስፋታቸው ፡ 1.7 ሜትር በ 1.8 ሜትር ሲሆኑ
- ✓ የማስታወቂያ ማሳያ መስታወት ስፋታቸው ፡ 1.6 ሜትር በ 1.7 ሜትር፣

- ✓ የሀይድሮሊክ ተከፋች በር እና ከታች ለመቆለፊያ የሚሆኑ ሁለት የማይዝግ ብረት ቁልፎች (Stainless steel lock) ያላቸው፣
- ✓ የብርሀን ሰጪ LED መብራቶች ያላቸው (ከመንገድ ዳር መብራቶች ሀይል ተሰበላቸው)፣

**ዓይነት 2**

- ✓ የሳጥን ስፋታቸው ፡ 1.05 ሜትር በ 2.1 ሜትር ሲሆኑ በዐይነት 1 መጠለያዎች ላይ ብቻ የሚገኙ ሲሆን ከመጠለያዎቹ በቀኝ ጎን በኩል ይገኛሉ፣
- ✓ የማስታወቂያ ማሳያ መስታወት ስፋታቸው 1.6 ሜትር በ1.7 ሜትር፣
- ✓ የሀይድሮሊክ ተከፋች በር ያላቸው እና ከታች አንድ የማይዝግ ብረት ቁልፍ (Stainless steel lock) ያላቸው
- ✓ የብርሀን ሰጪ LED መብራቶች ያላቸው (ከመንገድ ዳር መብራቶች ሀይል ተሰበላቸው)፣




## 1.36 በተንቀሳቃሽ አካላት ላይ የሚሰቀሉ ማታወቂያዎች

### 1.36.1 በተንቀሳቃሽ አካላት የላይኛው ክፍል ላይ የሚሰቀሉ ማታወቂያዎች:

- ✓ የመኪናን እንቅስቃሴ በማያውክ መልኩ በቀላል ቁስ መሰራት ይኖርባቸዋል፣
- ✓ እይታን እንዳይጋርዱ ቁመታቸው ወደላይ ከ ሀምሳ ሳንቲም መብለጥ የለበትም፣

### 1.36.2 በተንቀሳቃሽ አካላት ከጎን የሚሰቀሉ ማስታወቂያዎች

- ✓ መኪናው ላይ ለእይታና ለብርሀን ተብለው የተቀመጡትን ተካፋቾች መሸፈን የለበትም፣
- ✓ ከተካፋቾች ውጪ የመኪናውን አካል ሰባ በመቶ ብቻ እንዲሸፍኑ ይፈቀዳል፣







### 1.36.3 በተሽከርካሪ ዉስጥ በዲጂታል ቴክኖሎጂ የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች

በተሽከርካሪዎች ውስጥ በዲጂታል ቴክኖሎጂ የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች የሚሞሪ ካርዶች፣ ፍላሽና መሰል ኤሌክትሮኒክስ መረጃ አስተላላፊዎችን በመጠቀም መልእክት በስክሪኑ በማስተላለፍ ምርትንና አገልግሎትን ለማስተዋወቅ ይረዳል።

የማስታወቂያ ማስነገሪያው ወይም ማሳያ ስክሪን መጠንም (15 inch, 17 inch, 18.5 inch, 19 inch, 22 inch, 24 inch, 26 inch, 32 inch ወዘተ) መሆን ይኖርበታል።



**1.37 በኤሌክትሮኒክስ ስክሪን ለሚሰራጭ ማስታወቂያ**

- ✓ ስክሪኖቹ ከእግረኛ ማቋረጫዎች እንዲሁም ከመስቀለኛና አደባባዩች 20 ሜትር መራቅ አለባቸው፤
- ✓ በሁለት ስክሪኖች መካከል ቢያንስ የ1 ሜትር ርቀት ሊኖር ይገባል፤
- ✓ ውቅር /Structure/ የሚፈቅደው መሆኑ መረጋገጥ አለበት፣
- ✓ የድጅታል ማስታወቂያው ውቅር ትንተና /Structural Analysis/ መቅረብ አለበት /ለትልልቅ ስክሪን/፣
- ✓ ዴሲቤል በላይ ድምፁ የማይረብሽ እና ዝቅተኛ የኃይል ፍጆታ ሊኖረው ይገባል፤
- ✓ በቀላሉ ለጥገና አመቺ መሆን አለበት፤
- ✓ እጅግ በጣም ጥሩ የምስል ጥራት እና ተመጣጣኝ የብርሃን መጠን ሊኖረው ይገባል ፤
- ✓ ለተጠቃሚ ምቹ የሆነ እና የተለያዩ የፈጠራ ቅርጾች ያካተተ ቢሆን፤

ዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ ማለት የግለሰቦችን ወይም የድርጅቶችን የማይንቀሳቀስ ወይም ተንቀሳቃሽ ምስሎችን በማስታወቂያ በከፍተኛ ጥራት ግራፊክስ የሚያሳይ የኤሌክትሮኒክስ የዉጭ ማስታወቂያ ሚዲያ አይነት ነው። ዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ ማስቀመጥ ሲፈለግ /ሲመረጥ/ የሚከተሉት ሁኔታዎች ከግምት ውስጥ ማስገባት አለበት።

**1.37.1 ለአካባቢዉ ተስማሚ መሆናቸውን በተመለከተ**

ዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ የት እንደሚገኝ ለመወሰን በሞቃት ወይም በቀዝቃዛ የአየር ሙቀት፣ እንዲሁም በዝናብ፣ በበረዶ፣ በነፋስ፣ በአቧራ ወይም በእርጥበት ሁኔታ እንዴት እንደሚሰራ ማጤን ሊኖርብን ይገባል። እንዲሁም የስክሪን ዲዛይን እና ማቀፊያው ለኤልኢዲዎች ቀጣይ ስራ እና ረጅም ጊዜ መቆየቱ ወሳኝ ነው።

**1.37.2 የእይታ ጥራት በተመለከተ**

የዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ የተመልካቹን ትኩረት የማይረብሽ እና ስለምርቱ መልእክት ብቻ የሚያስተላለፍ መሆን አለበት። እንዲሁም ብሩህ፣ እይታን የማይረብሽ እና ቀለሞችን በትክክል ማሳየት የሚችል መሆን ይኖርበታል። የፒክሰል መጠን በRGB ፒክስሎች መካከል ያለው ቦታ ሲሆን የፒክሰል መጠን በጣም ትልቅ ከሆነ የእይታ ጥራትን ይቀንሳል።

**1.37.3 የብርሃን መጠን በተመለከተ**

ዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ እስከ 5,000 nits (ስክሪኑ በእያንዳንዱ ካሬ ሜትር ሊያወጣ የሚችለዉ የሻማ ሙብራት) የሚመከር ሲሆን በቀጥታ የፀሐይ ብርሃን ላይ ላሉ ደግሞ 5,000+ nits ይመከራል።

### 1.37.4 ለደህንነት ትኩረት ከማድረግ አንጻር

የዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ ድምቀቱ ዋና የደህንነት ስጋት ሊሆን ይችላል። ስለሆነም በጣም ደማቅ የሆነ ስክሪን አሽከርካሪዎችን ትኩረቱን ሊከፋፍል እና በምሽት ለመንዳት አስቸጋሪ ሊሆን ስለሚችል የLED ማሳያዉ በአካባቢዉ ባለው ብርሃን መሰረት የስክሪኑን ብሩህነት እና ድምቀት ዝቅ ለማድረግ፣ ለምሳሌ በምሽት ላይ ያለውን ደማቅነት ለመቀነስ LED በራሱ የማደብዘዝ አቅም ያላቸዉ መሆን አለባቸዉ።

### 1.37.5 ጥገና እና አገልግሎት በተመለከተ

የዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ ሲሰራ ሁል ጊዜ ጥሩ መስሎ እንዲታይ እና በተቻለ መጠን ረጅም ጊዜ እንዲቆይ ለማድረግ መደበኛ ጥገና ወሳኝ ነው።

### 1.37.6 ስፋትና መጠንን በተመለከተ

- ✓ የኤሌክትሮኒክስ ዲጂታል የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳዎች የማይለዋወጡ ኤሌክትሮኒክስና የታተሙ ምልክቶችን ይተካሉ፣
- ✓ ሙሉ በሙሉ በኮምፒዩተር ቁጥጥር ስር ያሉ፣ ዲጂታል ቢልቦርዶች ምስሎችን፣ ቪዲዮና አኒሜሽን ማሳየት ይችላሉ። እንዲሁም ለተመሳሳይ የማሳያ ስርዓት ለብዙ አስተዋዋቂዎች እቃዎችን እና አገልግሎቶችን በማስተዋወቅ መልእክታቸውን ሙሉ በሙሉ በመለዋወጥ ይቀርባሉ።
- ✓ ምስሎችን በመለዋወጥ የተለያዩ የውጭ ማስታወቂያዎችን ማስተላለፍ ይችላል። እነዚህ የማስታወቂያ ሰሌዳዎች በዋነኛነት በውጭ ማስታወቂያ ህግ ለሕዝብ አገልግሎት ዓላማዎችም ሊያገለግሉ ይገባል።
- ✓ ዲጂታል ቢልቦርዶች ለማስታወቂያዎች ከፍተኛ ትውስታን እና የሸማቾችን አወንታዊ አመለካከቶች ያመነጫሉ።

**የዲጂታል ስፋት= የአንድ ዲጂታል ፓኔል ስፋት 1ሜx1ሜ ተገጠጥሞ ዲጂታል LED የውጭ ማስታወቂያ የሚሰራ በመሆኑ እንደጠያቂው ፍላጎት የሚወሰን ይሆናል፣**

**ከመሬት በላይ ቁመት= 3.0 ሜትር**

**የመሸፈኛ ቁሳቁስ= የብረት መዋቅር፣ galvanized Plate እና ጠንካራ የፓነል መስታወት**






በአዲስ አበባ ከተማ ያለውን የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥና አተገባበር በስታንዳርድ ባለመመራቱ እንዲሁም በዘርፉ የተሰማሩ ባለድርሻ አካላትና የመንግስት ተቋማት ባለ መቀናጀታቸውና ሚናቸውን ባለማወቃቸው በዘርፉ የሚፈለገውን ውጤት ማምጣት አልተቻለም። በዚሁ መሰረት የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥና ቁጥጥርን በተመለከተ ከዚህ በታች የተገለፁ ተቋማት ተቀናጅተው መስራት እንደሚገባቸው ተግባርና ኃላፊነታቸው ተቀምጧል።

### 1.38 በተሽከርካሪ ላይ በድምጽ፣ በምስል ወይም በስዕል የሚተላለፍ የውጭ ማስታወቂያ

#### 1.38.1 በተሽከርካሪ ላይ የሚለጠፍ ማስታወቂያ

1. ማንኛውም ሰው በንግድ ተሽከርካሪው ላይ የራሱን ምርትና አገልግሎት ማስተዋወቅ ይችላል
2. ለሕዝብ አገለግሎት በሚውሉ ተሽከርካሪዎች ላይ ማስተዋወቅ የሚችለው የማስታወቂያ ወኪል ብቻ ነው
3. በተሽከርካሪ ላይ የሚለጠፍ የውጭ ማስታወቂያ እይታን በማይከልልና ብርሃን አስተላላፊ በሆነ ቁስ መሆን አለበት። ሆኖም በተሽከርካሪው ፊትና ኋላ መስታወት ላይ መለጠፍ የተከለከለ ነው።
4. በተሽከርካሪው ውስጥ የማስታወቂያ ወኪሉ ስምና አድራሻ፣ የፈቃድ ቁጥሩ፣ ፈቃዱን የሰጠው አካልና ፈቃዱ የሚያበቃበት ጊዜ ሁልጊዜ መያዝ ያለበት ሲሆን በተጠየቀ ጊዜ ማሳየት አለባቸው።
5. ከተከፋቾች ውጭ የመኪናውን ሰባ በመቶ ብቻ እንዲሸፍኑ ይደረጋል

#### 1.38.2 በተሽከርካሪ ላይ በድምጽ የሚተላለፍ ማስታወቂያ

1. በዚህ መንገድ ማስተዋወቅ የሚቻለው ወቅታዊ ጉዳይን በተመለከተ ለሰሚናር፣ ለኤግዚቢሽን፣ ለሙዚቃ ኮንሰርት፣ እና ለምርጫ ቅስቀሳ እንዲሁም ሌሎች ወቅታዊ ጉዳዮች ሲሆን ምርትና አገልግሎት ማስተዋወቅ የተከለከለ ነው። ሆኖም በህመም ምክንያት በተሽከርካሪ በድምጽ እርዳታ የሚጠይቁ ከሆነ ከሆስፒታል በሚያመጡት ማስረጃ መሠረት በልዩ ፈቃድ ፈቃድ ሊሰጣቸው ይችላል።
2. በተሽከራካሪ ላይ በድምጽ የሚተላለፍ ማስታወቂያ ማስተዋወቅ የሚቻለው ከጧቱ 2፡00ሁለት እስከ ቀኑ አስራ ሁለት ሰዓት(12፡00) ድረስ ብቻ ነው።
3. በትምህርት ቤቶች፣ በሆስፒታሎች፣ በፍርድቤቶች፣ ሕዝባዊና ሃይማኖታዊ በዓላት በሚካሄድበት አካባቢ ወይም ከፍተኛ ድምጽ ያውካቸዋል በሚባሉ ተቋማት አካባቢ ማስተዋወቅ አይፈቀድም።
4. የድምጹ መጠን ከ50 ዴሲቤል መብለጥ የለበትም።
5. በተሽከርካሪ ላይ በድምጽ ወይም በድምጽና በምስል የማስተዋወቅ ስራ የሚሰሩ ግለሰቦች ወይም ድርጅቶች ከግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን ፈቃድ ማግኘታቸውን እና በተፈቀደው ሰዓትና ቦታ

ብቻ ማስተዋወቃቸውን የአዲስአበባ ከተማ አስተዳደር የትራፊክ ጽህፈት ቤት ይቆጣጠራል፤ አስፈላጊውን እርምጃ ይወስዳል።

6. በተሽከርካሪ ዉስጥ በዲጂታል ቴክኖሎጂ የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች

7. በተሽከርካሪዎች ውስጥ በዲጂታል ቴክኖሎጂ የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች የሚሞሪ ካርዶች፣ ላሽና መሰል ኤሌክትሮኒክስ መረጃ አስተላላፊዎችን በመጠቀም መልእክት በስክሪን በማስተላለፍ ምርትንና አገልግሎትን ማስተዋወቅ ይቻላል

### 1.39 በባለሙብራት ሳጥን ስለሚዘጋጅ የውጭ ማስታወቂያ

1. በባለሙብራት ሳጥን ተዘጋጅቶ በመሬት ላይ በቋሚ ምሰሶ ወይም በሕንፃ አካል ላይ የሚተከል ወይም የሚቀመጥ የውጭ ማስታወቂያ

   ሀ. በቀላሉ በእሳት በማይያያዝ መሳሪያ መሰራት ይኖርበታል

   ለ. የራሱ የኤሌክትሪክ መስመር፣የኤሌክትሪክ ኮንዳክተር ወይም ኮንዲውትና መቆጣጠሪያ ሊኖረው ይገባል

2. በባለሙብራት ሳጥን ተዘጋጅቶ በመሬት ላይ በቋሚ ምሰሶ ወይም መሰል አካል ላይ የሚተከል እና በህንፃ ላይ የሚሰቀል ማስታወቂያ

   - ✓ በመሬት ላይ ስፋቱ ከ6 ካሬ ሜትር መብለጥ የለበትም
   - ✓ በህንፃ ላይ ስፋቱ ከ4 ካሬ ሜትር መብለጥ የለበትም
   - ✓ ቁመቱ ከ1.5 ሜትር ያላነሰ እና ወርዱ ከ3 ሜትር ያልበለጠ መሆን የለበትም
   - ✓ በህንፃ ላይ የሚሰቀል ቁመቱ ከ0.5 ሜትር ያላነሰ እና ወርዱ ከ3 ሜትር ያልበለጠ መሆን አለበት

3. በባለሙብራት ሳጥን የተዘጋጀ ማስታወቂያ ወይም ማናቸውም ብርሃን የሚጠቀም የማስታወቂያ ሠሌዳ ስፋቱ

   - ✓ ከ0.5 ካሬ ሜትር በታች ከሆነ የሚቆመው የብርሃን ሃይል መጠን ከ1000 ሻማ በሜትር ካሬ
   - ✓ ከ0.5 ካሬ ሜትር እና 2 ሜትር ካሬ መካከል ከሆነ የሚጠቀመው የብርሃን ሃይል መጠን ከ800 ሻማ በሜትር ካሬ፣መብለጥ የለበትም።
   - ✓ በ2 ካሬ ሜትር እና በ10 ሜትር ካሬ መካከል ከሆነ የሚጠቀመው የብርሃን ሃይል መጠን ከ600 ሻማ በሜትር ካሬ መብለጥ የለበትም።

### 1.40 በጨርቅ ወይም በሸራ ባነር፣ወይም መሰል ነገር የሚዘጋጅ ተንጠልጣይ የውጭ ማስታወቂያ

1. በኤሌክትሪክ ወይም በስልክ ምሰሶ ላይ ባነርን በማንጠልጠል ወይም በመወጠር ማስተዋወቅ የተከለከለ ነው።

2. በጨርቅ ወይም በሸራ ባነር፣ወይም መሰል ነገር የሚሰቀል ወይም የሚንጠለጠል የባነር ማስታወቂያ ፈቃድ ሲሰጥ

   - ✓ ወቅታዊ ሁኔታዎች ብቻ ለማስተዋወቅ መሆን አለበት
   - ✓ ለምርትና አገልግሎት ማስታወቂያነት መዋል የለበትም
   - ✓ የቆይታው ጊዜ ወቅታዊ ሁኔታው ከመጀመሩ ከአንድ ወር በላይ እንዲሁም ከተጠናቀቀ በኋላ ከአንድ ሳምንት በላይ መቆየት የለበትም፡
   - ✓ በአደባባይ ላይ ባነር በማንጠልጠል ወይም በመወጠር ማስተዋወቅ አይቻልም። ሆኖም ከባለስልጣን መ/ቤቱ ጋር በሚደረግ ስምምነት ለህዝብ አገልግሎት ለሚውል ማስታወቂያ ሊፈቀድ ይችላል
   - ✓ የማህበራዊ ተቋማት የሚሰቅሉት ባነር እስከ አንድ ወር ከ15 ቀን ድረስ በክፍያ መስቀል ይችላሉ

### 1.41 በበራሪ ወረቀቶች የሚሠራጭ የውጭ ማስታወቂያ

በፓስተር፣ በአነስተኛ ስቲከር፣ በተባዛ በራሪ ወረቀት ወይም በብሮሸር፣ በሊፍሌት፣ በፍላየር፣ በስቲከር፣በወረቀት ማስታወቂ እና መሰል ሁኔታ የሚዘጋጅ የውጭ ማስታወቂያ ሲሆን

1. መለጠፍ የሚቻለው ለዚህ አገለግሎት ተብለው በተዘጋጁ የየውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳዎች ብቻ መሆን አለበት
2. በግድግዳ ላይ ወይም በአጥር ላይ ወይም በአውቶቡስ ፌርማታ ወይም በስልክና በኤሌክትሪክ ምሰሶ ወይም መሰል አገለግሎት መስጫ ላይ መለጠፍ ወይም ማጣበቅ የተከለከለ ነው
3. የተባዙ በራሪ ማስታወቂያዎችን ከአየር ወደ መሬትም ሆነ በመሬት ላይ በመበተን ማስተዋወቅ የተከለከለ ነው
4. በዚህ አንቀጽ 23.2 እና 23.3 የተደነገገው ድንጋጌ ለትርፍ ባልተቋቋመ የመንግስት መሥሪያ ቤት በሚሰራጭ የሕዝብ ማስታወቂያ ላይ ተፈፃሚ አይሆንም
5. በብሮሸርና መሰል በራሪ ወረቀቶች የሚሠራጭ የውጭ ማስታወቂያ የሚተዋወቅለት ድርጅት ለሚተላለፈው መልዕክት ኃላፊነት አለበት

### 1.42 በጎዳና እቃዎች ላይ ስለሚቀመጥ የውጭ ማስታወቂያ

በአውቶቢስ ፌርማታ በሚገኙ መጠለያዎች፣ በአትክልት መከለያዎች፣ በቆሻሻ ማጠራቀሚያ ፣ ህዝብ መፀዳጃ ቤትና መሰል የጎዳና እቃዎች ላይ የሚለጠፍ ወይም በማናቸውም መንገድ የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ

- ✓ የእቃዎችን አገልግሎት አሰጣጥ የሚያሰናክል ወይም የሚያውክ ሁኔታ መለጠፍ ወይም መቀመጥ የለበትም
- ✓ የትራፊክ እንቅስቃሴን በሚገታ ወይም ደኅንነቱን በሚቀንስ ሁኔታ መሰራጨት የለበትም
- ✓ የሚለጠፍ ወይም የሚሰቀል ማስታወቂያ ስፋት/መጠን/ አዲስ በወጣው ስታንዳርድ መሰረት ይሆናል

### 1.43 በተንሳፋፊ ፊኛ፤ በኬብል የሚንሸራተትና መሰል ነገር ላይ የሚሰራጭ ማስታወቂያ

1. በተንሳፋፊ ፊኛ፣ ውል ብልቢትና መሰል ተንሳፋፊ ነገር ላይ የተዘጋጀ የውጭ ማስተወቂያ በአየር ላይ እንዲንሳፈፍ ሲደረግ የአውሮፕላን ደህንነትን አደጋ ላይ የሚጥል መሆን የለበትም
2. በተንሳፋፊ ፊኛ፣ ውል ብልቢትና መሰል ተንሳፋፊ ነገር ላይ የተዘጋጀ የውጭ ማሰተወቂያን በአየር ላይ ለማንሳፈፍ የማስታወቂያ አስነጋሪው፣ አዘጋጁ ወይም አሰራው በቅድሚያ አግባብ ካለው አካል የተፈቀደለት መሆን አለበት
3. በተነሳፋፊ ፊኛ፣ ውል ብልቢትና መሰል ተንሳፋፊ ነገር ላይ የተዘጋጀ የውጭ ማስተወቂያን
4. በሚመለከተው አካል ከተፈቀደው ከፍታ በላይ በአየር ላይ ማንሳፈፍ የተከለከለ ነው
5. በሚመለከተው አካል በተከለከለ የአውሮፕላን ማረፊያ ክልል ውስጥ ማንሳፈፍ እና በማናቸውም መንገድ ላይ ሆኖ እንዲንሳፈፍ ማድረግ የተከለከለ ነው
6. በኬብል በሚንሸራተት የሚሰራ ማስታወቂያ
   - ✓ ሌላ የተዘረጋ መሰረተ ልማትን የማያውክ፤ የማይከለክልና የማያደናቅፍ መሆን አለበት
   - ✓ በአካባቢው በሚኖሩ ግንባታወች ላይ ከፍተኛ የእይታ ክልከላ የማያደርግ መሆን አለበት

## ማስፈፀሚያ ስልቶች

በአዲስ አበባ ከተማ ያለውን የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥና አተገባበር በስታንዳርድ ባለመመራቱ እንዲሁም በዘርፉ የተሰማሩ ባለድርሻ አካላትና የመንግስት ተቋማት ባለ መቀናጀታቸውና ሚናቸውን ባለማወቃቸው በዘርፉ የሚፈለገውን ውጤት ማምጣት አልተቻለም። በዚሁ መሰረት የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ አሰጣጥና ቁጥጥርን በተመለከተ ከዚህ በታች የተገለፁ ተቋማት ተቀናጅተው መስራት እንደሚገባቸው ተግባርና ኃላፊነታቸው ተቀምጧል።

- ➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ኮሙኒኬሽን ቢሮ፣**

- በከተማዋ የሚተከሉ ማስታወቂያዎች ይዘታቸው ከማህበረሰቡ ባህልና ወግ ጋር የሚጣጣሙ መሆኑን ይከታተላል፤
- የማስታወቂያ ስራ ለመስራት ለሚፈልጉ ማንኛውም ሰው የሙያ ብቃት ማረጋገጫ ፈቃድ ይሰጣል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን፣**

- በስታንዳርዱ መሰረት የማስታወቂያ ፈቃድ ይሰጣል፤
- በተቀመጠው ስታንዳርድ መሰረት ተግባራዊ መሆኑን ይከታተላል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር መንገዶች ባለስልጣን፣**

- በመንገዶች ዳርቻና ድልድዮች ላይ የሚሰጡ የማስታወቂያ ቦታዎችን በተመለከተ ይገመግማል፤
- በድጋፍ ግንብ ግድግዳዎች እና በድልድይ መሰሶዎች ላይ የሚሳሉ የማስታወቂያ ስዕሎች በተመለከተ ይሁንታ በመግለፅ በባለስልጣኑ በኩል ፍቃድ ይሰጣል፣

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር መሬት ልማትና አስተዳደር ቢሮ፣**

- ለማስታወቂያ አግልገሎት የሚውሉ ቦታዎችን በተመለከተ ከይገባኛል ጥያቄ ነፃ መሆናቸውን አጣርቶ በጊዜያዊነት ቦታ ይሰጣል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ባህል ኪነ-ጥብና ቱሪዝም ቢሮ፣**

- በከተማዋ የሚሰቀሉ፣የሚለጠፉ እና የሚዘዋወሩ ማስታወቂያዎች ከህበረተሰቡ ባህልና ታሪክ ያፈነገጡ እንዳይሆኑ ከሚመለከታቸው ተቋማት ጋር በቅንጅት ይሰራል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ትራፊክ ማኔጅመንት ኤጀንሲ፣**

- በመንገድ ዳር የሚተከሉ ማስታወቂያዊች ከትራፊክ ደህንነት አንፃር አግባብ መሆናቸውን ይከታተላል፣ ይቆጣጠራል፤
- በተንቀሳቃሽ ተሸከርካሪዎች የሚነገሩ ማስታወቂያዎች ፈቃድ ያላቸው መሆኑን ይቆጣጠራል፤
- በድምጽ የሚተላለፉ ማስታወቂያዎች በአካባቢ ጥበቃ ባለስልጣን በኩል ይሁንታ ካገኘ በኋላ በኤጀንሲው በኩል ክትትል በማደረግ የቅንጅት ስራ ይሰራል፣
- የትራፊክ ምልክቶች እና የትራፊክ አመላካቾች በትራፊክ ማኔጅመንት ስታንዳርድ መሰረት ያለፈቃድ የሚተከሉ ይሆናሉ፣

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ውበትና አረንጓዴ ልማት ቢሮ፣**

- ለአረንጓዴ ቦታነት በተከለሉ ቦታዎች በህገ ወጥ መንገድ የተተከሉ ማስታወቂያዎችን በተመለከተ ከሚመለከታቸው አካላት ጋር በመሆን ቁጥጥር ያደርጋል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር የአካባቢ ጥበቃ ባለስልጣን፣**

- በተንቀሳቃሽ ተሸከርካሪዎች የሚነገሩ ማስታወቂያዎችን የድምፅ ብክለት ይከታተላል፣ ይቆጣጠራል፤

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ትራንስፖርት ቢሮ፣**

- የአውቶብስ መጠበቂያ መጠለያዎች ላይ የሚገኙ የውጭ ማስታወቂያ መለጠፊያ ሳጥኖችን ላይ የሚለጠፉ ማስታወቂዎች በግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን ፈቃድ በማግኘት አገልግሎት እንዲውል ይደረጋል፣

➢ **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ንግድ ቢሮ፣**

- የማስታወቂያ ስራ ለመስራት ለሚፈልጉ ማንኛውም ሰው የንግድ ፈቃድ ከመስጠቱ በፊት የሙያ ብቃት ማረጋገጫ እንዲያቀርቡ ይጠይቃል፣ሲያሟሉ ፈቃድ ይሰጣል፤

- **የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ደንብ ማስከበር ባለስልጣን፣**
  - በህገ ወጥና ከስታንዳርድ ውጪ የተተከሉ ማስታወቂያዎች ላይ እርምጃ ይወስዳል፤
  - ጊዜያቸው ያለፈባቸውን እና ባለቤት የሌላቸው ማስታወቂያዎች ከሚመለከታቸው አካላቶች ጋር በመሆን እንዲነሱ ያደርጋል፤
  - ባልተፈቀዱ ቦታዎች የሚተከሉ ማስታወቂዎች የከተማዋን ገፅታ ስለሚያበላሹ ተከታትሎ አግባብ ባለው ህግ እርምጃ ይወስዳል፤
- **ፍትህ ቢሮ፣**
  - በህግ አግባብ ሊታዩ የሚችሉ ጉዳዮችን በተመለከተ ክትትልና ድጋፍ ያደርጋል፤
  - ህገወጥ የዉጭ ማስታወቂያ የሚለጥፉ እና የሚሰቅሉ ግለሰቦችና ድርጅቶች ተጠያቂ እንዲሆኑ ከህግ አስከባሪ አባላት ጋር በመሆን ክስ በመመስረት ተባባሪ ሊሆኑ ይገባል፣
- **ቀላል ባቡር ኮርፖሬሽን**
  - የውጭ ማስታወቂያ አስነጋሪ ተቋማት በቀላል ባቡር ውስጥ እና በባቡሩ የውጭ ገፅታ ላይ እንዲሁም በባቡር መጠበቂያና ሀዲድ ድልድዮች ላይ ማስተዋወቅ ሲፈልጉ ከግንባታ ፍቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን ፈቃድ ማውጣት እንዳለባቸው ማሳወቅ ይኖርባቸዋል፣
- **የኢትዮጵያ ማስታወቂያ ስራ ማህበር**
  - የማስታወቂያ ስርአትን በጠበቀ መልኩ ስራዎች እንዲከናወኑ ለአባላቶቻቸው የግንዛቤ ስራ ማከናወን እና ያለፍቃድ ማስታወቂያዎች እንዳይሰቀሉ እንዳይለጠፉ ወይም እንዳይንጠለጠሉ በማህበሩ በኩል ክትትል ያደርጋል፣

## ክፍል ዘጠኝ

## ልዩ ልዩ ድንጋጌዎች

### 1.44 የመተባበር ግዴታ

ማንኛውም ሰው ይህን መመሪያ በማስፈጸም ረገድ የመተባበር ግዴታ አለበት።

### 1.45 የውጭ ማስታወቂያን አለአግባብ ስለማስወገድ

ማንኛውም ሰው ፈቃድ በማግኘት የተተከለ፣ የተለጠፈ ወይም በማናቸውም መንገድ የተሰራጨ ሕጋዊ የውጭ ማስታወቂያን ሆነ ብሎ የማስታወቂያ አስነጋሪውን ለመጉዳት በማሰብ ማስወገድ የለበትም።

### 1.46 አቤቱታ ስማቅረብ

1. ከውጭ ማስታወቂያ ጋር በተያያዘ የዚህን መመሪያና የደንቡን ድንጋጌዎች በመተላለፍ በተሰራጨ ማንኛውም ማስታወቂያ መብቱ የተጣሰ ሰው የማስታወቂያው ስርጭት ፈቃድ እንዲታገድለትና ማስታወቂያው እንዲወገድለት ለፈቃድ ሰጪው አቤቱታ ማቅረብ ይችላል፣
2. የዚህ አንቀጽ 30(1) ድንጋጌ ሥልጣን ላለው የዳኝነት አካል ክስ ማቅረብን የሚከለክል አይሆንም።

### 1.47 ይግባኝ ስለማቅረብ

1. በፈቃድ ሰጪው ስር በየደረጃው ባሉ አስፈፃሚ አካላት  በተሰጠው ማናቸውም ውሳኔ ላይ አቤቱታ ያለው ሰው ውሳኔ ከተሰጠበት ቀን አንስቶ በ15 የሥራ ቀናት ውስጥ አቤቱታውን በፅሁፍ ለባለሠልጣኑ ማቅረብ ይችላል፣
2. ፈቃድ ሰጪው የአመልካቹ አቤቱታ በደረሰው ከ30 ቀናት ባነሰ ጊዜ ውሳኔ መስጠት ይኖርበታል፣

3. ሥልጣን ለተሰጠው የመንግሥት አካል ይግባኝ የማቅረብ መብቱ እንደተጠበቀ ሆኖ በባለስልጣኑ የሚሰጠው ውሳኔ የመጨረሻ ይሆናል።

**1.48 የመሸጋገሪያ ድንጋጌ**

1. ይህ መመሪያ ከመውጣቱ በፊት በሕግ መሰረት ፈቃድ ተሰጥቶት እና የአገልግሎት ክፍያ ተከፍሎበት የተተከለ፣ የተለጠፈ ወይም በማናቸውም መንገድ የተሰራጨ የውጭ ማስታወቂያ የደንቡን እና የመመሪያውን ድንጋጌዎች የሚያሟላ ከሆነ በዚህ መመሪያ መሰረት ፈቃድ እንዳገኘ ይቆጠራል፣

2. ይህ መመሪያና ደንቡ ከመውጣቱ በፊት ፈቃድ ሳይሰጠው ወይም ፈቃድ ቢሰጠውም የአዋጁን፣ የደንቡንና የመመሪያ ድንጋጌዎች የማያሟላ የውጭ ማስታወቂያ የተከለ ወይም በማናቸውም መንገድ ያሰራጨ የማስታወቂያ ሥራ ወይም አሰራጭ፥

   ሀ. ይህ መመሪያ ከፀደቀበት ቀን ጀምሮ በ1 ወር ጊዜ ውስጥ የውጭ ማስታወቂያው እንዲሰራጭ ማመልከቻውን በፅሁፍ ለባለስልጣኑ ማቅረብ እና የተሰራጨው የውጭ ማስታወቂያ የዚህን መመሪያና የደንቡን ድንጋጌዎች አሟልቶ ከተገኘ ማስታወቂያው እንዲሰራጭ የተፈቀደለትና የተመዘገበ መሆኑን የሚገልፅ ማስረጃ መያዝ እና ለማስታወቂያው የተወሰነውን ክፍያ መክፈል አለበት፣

   ለ. የተሰራጨው የውጭ ማስታወቂያ የዚህን መመሪያና የደንቡን ድንጋጌዎች ባለማሟላቱ እንዲሰራጭ ፈቃድ ካላገኘ ማስታወቂያውን ማንሳት ወይም ማስወገድ አለበት፣

3. ይህ መመሪያና ደንቡ ከመውጣቱ በፊት ለውጭ አገር ዜጋ በውጭ ማስታወቂያ ሥራ እንዲሰማራ እና የሌሎችን ሰዎች የውጭ ማስታወቂያ እንዲያሰራጭ የተሰጠ ፈቃድ መሰረዝ ይኖርበታል፣

4. በዚህ አንቀፅ ንዑስ አንቀፅ (3) መሰረት የውጭ ማስታወቂያ ስርጭት ፈቃዱ የተሰረዘበት የውጭ አገር ዜጋ ወይም ድርጅት ይህ መመሪያና ደንቡ ከመውጣቱ በፊት ተክሎ ለሌላ ሰው የሚያከራየውን የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳ ፍሬም፣ የውጭ ማስታወቂያ መለጠፊያ ሳጥን ወይም ቦርድ ወይም መሰል የውጭ ማስታወቂያ ማሰራጫ መሳሪያ ወይም ተያያዥ ንብረቶችን በማንሳት መውሰድ ወይም ለሌላ ሰው ማስተላለፍ ይችላል።

**1.49 አስተዳደራዊ እርምጃ ወይም ቅጣት**

በማስታወቂያ አዋጁ ቁጥር 759/2004 የተደነገገው ቅጣት እንደተጠበቀ ሆኖ የዚህ ደንብ ድንጋጌዎችን በመተላለፍ ጥፋት የፈፀመ ማንኛውም ሰው ፡-

1. በዚህ መመሪያ መሰረት የአገልግሎት ክፍያ በሚከፈልበት ጊዜ ውስጥ የሚፈለግበትን የአገልግሎት ክፍያ በሙሉ ያልከፈለ ማንኛውም ሰው ክፍያውን ማጠናቀቅ ካለበት ከመጨረሻው ቀን በኋላ ክፍያውን ላዘገየበት ለእያንዳንዱ ወር ከሚፈለግበት የአገልግሎት ክፍያ ከመቶ አስር ፐርሰንት መቀጮ እየተጨመረበት ይከፍላል

2. የዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ (1) መሠረት ሳይከፍል ከሁለት ወራት በላይ ከቆየ ግንባታ ፈቃድ ሰጭው የውጭ ማስታወቂያ ሰሌዳውን በማንሳት ይወርሳል፣ ያነሳበትንም ወጪ በህግ ይጠይቃል፣

3. የዚህን መመሪያ ወይም ሌሎች ህጐች ድንጋጌ ባለማክበር የውጭ ማስታወቂያ በደንብ ማስከበር ባለስልጣን አማካይነት የተነሳበትና ለዚሁ የወጣውን ወጪ የከፈለ ሰው በከተማው ክልል በማንኛውም ቦታ የውጭ ማስታወቂያ ሥራ ወይም የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ ጥያቄ ቢያቀርብ ለአንድ ዓመት እንዳይስተናገድ ይታገዳል፣

4. ለአጭር ጊዜ በፖስተር፣ በስቲከር፣ በባነር ለሚለጠፍና ለሚንጠለጠል እንዲሁም በብሮሸር፣ በሊፍሌት፣ በራሪ ወረቀት የሚሰራጭ የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ ከተሰጠበት ጊዜ በተጨማሪ ለሚቆየው ለእያንዳንዱ ቀን የአገልግሎት ክፍያው ሁለት እጥፍ ይከፈልበታል። ሆኖም የሚቆይበት ጊዜ ከአንድ ሳምንት የሚበልጥ ከሆነ ባለስልጣኑ በራሱ ወጪ ያነሳዋል፤ ወጪውንም የማስታወቂያዉ ባለቤት እንዲተካ ያደርጋል፣

5. ያለፈቃድ ወይም ከተፈቀደለት ሰዓት ውጭ በመኪና ላይ የማስታወቂያ ሥራ ሲሰራ የተገኘ አሽከርካሪ ብር 1,600.00 (አንድ ሺህ ስድስት መቶ) ይቀጣል ማስታወቂያው በመኪናው ላይ የተለጠፈ ከሆነ እንዲያነሳ ይደረጋል፤

6. ማንኛውም ሰው የዚህን መመሪያና የደንብ ድንጋጌዎች ተላልፎ የተገኘ ብር 2,000.00 (ሁለት ሺህ ብር) መቀጮ ይከፍላል።

7. የዚህን መመሪያና የደንቡን ድንጋጌ በመተላለፍ ጥፋት የፈፀመ ማንኛውም ሰው በወንጀል ሕጉ መሠረት የሚያስቀጡት ሁኔታዎች ውጭ፣ በአደባባይ ወይም ሕዝብ በሚያየው ቦታ መልካም ሥነ-ምግባርን ወይም መልካም ጠባይን የሚነካ ድርጊት አስቦ የፈጸመ እንደሆነ፣ የተከለከሉ የውጭ ማስታወቂያዎችን ያሰራጨ እና ገድብ የተደረገባቸውን ማስታወቂያ እንዲሰራጭ ያደረገ ብር 4,000 (አራት ሺ ብር ) መቀጮ ይከፍላል።

8. በዚህ መመሪያና ደንብ የተሰጠውን ክልከላና ግዴታ ያልተወጣ ማንኛውም የሥራ ኃላፊ ወይም ሠራተኛ አግባብነት ባለው ሕግ መሠረት ተጠያቂ ይሆናል፣

**1.50 መመሪያው የሚጸናበት ጊዜ**

ይህ መመሪያ ከጥቅምት 01/2015 ዓ.ም ጀምሮ የጸና ይሆናል።

አዲስ አበባ ጥቅምት 01/2015 ዓ.ም

**ስጦታው አካለ (ኢ/ር)**

በአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር

የግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን

ዋና ዳይሬክተር

በአዲስ አበባ ከተማ
ግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለሥልጣን



ADDIS ABABA CITY
BUILDING PERMIT & CONTROL
AUTHORITY

ቁጥር:- ግፈቁባ/መፈዳ/____/____/2015

ቀን:- ____/____/2015 ዓ/ም

## የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ ምስክር ወረቀት

የባለቤት /አመልካች ስም ______ የድርጅቱ ስም ______ ስልክ ______

አድራሻ: ክ/ከተማ ______ ወረዳ ______ የአካባቢው ልዩ ስም ______ /የመንገድ/አደባባይ/ድልድይ/ ______

አካባቢያዊ ኮኦርዲኔት X ______ Y ______

አገልግሎት ዓይነት:- የውጭ ማስታወቂያው ስፋት ______ የውጭ ማስታወቂያው ዓይነት ______

በግል ይዞታ/ህንፃ ግድግዳ/አጥር ላይ ☐ ህንፃ አናት ላይ ☐ የሚተከል በብርሀን/በምስልና/ድምፅ/እና በዲጂታል ቴክኖሎጂ ☐

በተሽከርካሪ አካል ላይ ☐ ቦታ ባለሁለት /ሶስት ምሰል ☐ በግድግዳና ጣራ ላይ የሚሳል ስዕል ☐ የበረንዳ ጥላ/በፈርማታ/በነዳጅ ማደያ ☐

የከፈሉት ገንዘብ መጠን ______ ፈቃድ የተሰጠበት ቀን ______ ቃድ የሚያበቃበት ቀን ______

### የማስታወቂያ ይዘት

ማስታወቂያው
ይቻላል

በፎቶ ይለጠፍ

++

### ሳይት ፕላን

ከ base map 1988,1997, ላይ ማስገባት



**ከላይ በዝርዝር የተገለጸው የውጭ ማስታወቂያ ፈቃድ ጥያቄ ተመርምሮ የፈቃድ ምስክር ወረቀት ተሰጥቷል፡፡**

| ያዘጋጀው | ያረጋገጠው | ያፀደቀው |
|---|---|---|
| ስም ------------------------------ | ስም ---------------------------------- | ስም ----------------------------- |
| ፊርማ ----------------------------- | ፊርማ ----------------------------- | ፊርማ --------------------------- |
| ቀን--------------------------------- | ቀን---------------------------------- | ቀን----------------------------- |

**ማሳሰቢያ፡** ይህ ፍቃድ በሶስት ቅጂ ተዘጋጅቶ ዋናው ለባለቤቱ ሁለተኛው ቅጂ ለዳይሬክቶሬቱ/ለቡድኑ ሶስተኛው ለመዝገብ ቤት ይሆናል፡፡